## የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ
## ቤተ ክርስቲያን

# ሕገ ቤተክርስቲያን




ለመጀመሪያ ጊዜ ፳፻፲ወ፫ ዓ.ም ታተመ
አዲስ አበባ ኢትዮጵያ



## የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ
## ቤተ ክርስቲያን

# ሕገ ቤተክርስቲያን

ጥቅምት ፳፻፯ ዓም
አዲስ አበባ ኢትዮጵያ

## ማውጫ



ክፍል ዐራት
ስለቅዱስ ፓትርያርክ



ክፍል ዐራት
ስለቅዱስ ፓትርያርክ

## መግቢያ

### በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስ ቅዱስ አሐዱ አምላክ አሜን።

ዓለም ከተፈጠረ፣ ዘመን ከተቆጠረ እስከ ሙሴ ደብረ ሲና፣ በሕገ ልቡና ባልተጻፈ ሕግ፤

ከሙሴ ደብረ ሲና እስከ ዘመነ ሥጋዌ ልደተ ክርስቶስ፣ በሕገ ኦሪት በተጻፈ ሕግ፣ ከዘመነ ሥጋዌ ልደተ ክርስቶስ እስከ ዛሬ በይቀጥላልም እስከ ዓለም ፍጻሜ፣ በሕገ ወንጌል በተጻፈ ሕግ፣ ዓለም በእነዚህ ሦስት ዓበይት ሕግጋት በቅደም ተከተል ሲተዳደር የነበረ፣ ያለ፣ የሚኖር መሆኑ የታወቀ ነው ።

‹‹ሰማይ ወምድር የኀልፍ ወቃልየሰ ኢየኀልፍ›› ‹ሰማይና ምድር ያልፋል፣ ቃሌ ግን አያልፍም› ይላል የእግዚአብሔር ቃል (ማቴ. ፳፬፡፴፫)

እግዚአብሔር ዓለሙን ሁሉ የሚያስተዳድረው በቃሉ ነው፤ የእግዚአብሔር ቃል ሰማይንና ምድርን አሳልፎ የሚኖር ነው ።

‹‹ሣሩ ይደርቃል፣ አበባውም ይረግፋል፣ የአምላካችን የእግዚአብሔር ቃል ግን ለዘለዓለም ጸንቶ ይኖራል›› (ኢሳይያስ ፵፡፰)

ቤተ ክርስቲያናችን ትምህርተ ሃይማኖቱን ከእግዚአብሔር አምላክ፣ ከነቢያት፣ ከሐዋርያትና ከአበው ሊቃውንተ ቤተ ክርስቲያን ተቀብላ በማስተማር ትኖራለች፤ ቅዱሳት መጻሐፍት የተጻፉት፣ ለትምህርት፣ ለአምልኮተ

ከላይ እንደተጠቀሰው ክርስትና በኢትዮጵያ ከገባበት ጊዜ ጀምሮ ሀገራችን ኢትዮጵያ ቀደም ሲል በግዕዝ፣ በኋላም በአማርኛ ብሔራዊ ሥራዋን ስታከናውን የኖረችው፣ ቤተ ክርስቲያናችን ባዘጋጀቻቸው ቅዱሳት መጻሕፍት ነው፤ በአሁኑም ወቅት በተለያዩ መጻሕፍት፣ መጽሔቶች፣ ጋዜጦችና በመሳሰሉት ሁሉ እየታተሙ ለሕዝብ ማስተማሪያና መመሪያ የሆኑትም ቤተ ክርስቲያኒቱ ጠብቃ ባቆየችው ፊደል መሆኑን ትውልዱ ያወቀውና የሚያውቀው ጉልህ ታሪክ ነው ።

ቅድስት ቤተ ክርስቲያናችን የኢትዮጵያ ሕዝብ የየጊዜውን ሥልጣኔ ተከትሎ እንዲሔድና ስለሀገር ፍቅር፣ ስለነፃነት ጥቅም፣ ስለዳር ድንበር መከበር፣ ስለብሔራዊ ምንነት ከምትሰጠው የተቀደሰ ትምህርት ሌላ ለወገንና ለሀገር ትምክህት የሚሆኑ ጀግኖች ከታሪክ እንዲወለዱ ወቅቱ የሚፈቅደውን ታሪካዊና ሃይማኖታዊ ትምህርት በማዘጋጀት ስታስተምር የኖረች የኢትዮጵያ ባለውለታ ቤተ ክርስቲያናችን ናት፤ የአሁኑ ትውልድም የአባቶቹን ታሪክ ተከትሎ ሀገሩን፣ ነፃነቱን፣ ክብሩንና ሃይማኖቱን ጠብቆ እንዲኖር ቤተ ክርስቲያኒቱ ከማስተማር የተገታችበት ጊዜ የለም ።

ቤተ ክርስቲያናችን ይህን ሁሉ ስታከናውን የኖረችው፣ አሁንም እያከናወነች ያለችው ሐዋርያትና አበው ሊቃውንት በወሰኑት ፍትሕ መንፈሳዊና ቀኖና ቤተ ክርስቲያን ድንጋጌ መሠረትነት ነው፤ ከዚህ አንፃር፤

፩. ቤተ ክርስቲያናችን በተለያዩ ጊዜያት ያወጣቻቸው ሕግጋት ቢኖሯትም እነዚህን ሕግጋት፣ ከደረሰችበት ዕድገት አንፃር እነዚህን ሕግጋት መርምሮ ተገቢውን ማሻሻያ ማድረግ አስፈላጊ ሆኖ በመገኘቱ፤

፪. ቤተ ክርስቲያን የሚፈለግባትንና ጊዜው የሚጠይቀውን ኢኮኖሚያዊ፣ ማኅበራዊና መንፈሳዊ ተልዕኮ እንድትወጣ

ለማስቻል የሚያግዝ ጠንካራ የአስተዳደር ሥርዓት መዘርጋት እጅግ አስፈላጊ መሆኑን በመገንዘብ፤

፫. በቤተ ክርስቲያን የሚገኙ የተለያዩ የአስተዳደር አካላት በመካከላቸው ያለውን ግንኙነት፣ ሥልጣንና ተግባር በግልፅ ለይቶ በሕግ ማስቀመጥ በቤተ ክርስቲያኒቷ ውስጥ ጠንካራ የመልካም አስተዳደርን ሥርዓት ለመዘርጋት ወሳኝ ሚና ያለው መሆኑን በማመን፤

፬. የቤተ ክርስቲያን አገልጋዮችንና ሠራተኞችን መሠረታዊ መብትና ግዴታ በሕግ በማስቀመጥ በቤተ ክርስቲያን አስተዳደር ውስጥ የሚሰጡ ውሳኔዎችን ሕጋዊ በማድረግ አገልግሎትን ይሰጡ ዘንድ በራስዋ ሕግና ሥርዓት ስትመራ የኖረችው ቤተ ክርስቲያናችን፣ አሁንም እንደ ጊዜውና እንደወቅቱ ሁኔታ

- መንፈሳዊና ማኅበራዊ ተግባርዋን
- የአስተዳደርና የፋይናንስ አገልግሎቷን
- የልማትና ሐዋርያዊ ተልዕኮዋን በበለጠ አጠናክራ መቀጠል የሚያስችላትን፣ እስካሁን ድረስ ስትሠራባቸው የነበሩትን ሕጎች፣ ደንቦችና መመሪያዎች በማሻሻልና በማስተካከል የቤተ ክርስቲያኒቱን እምነትና ሥርዓት፣ ክብርና ልዕልና ለመጠበቅና ለማስጠበቅ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ቅዱስ ሲኖዶስ ቀጥሎ ያለውን ሕገ ቤተ ክርስቲያን አውጥቷል።

## ምዕራፍ አንድ
## ጠቅላላ

### አንቀጽ ፩
### አጭር ርእስ

ይህ ሕግ "በቅዱስ ሲኖዶስ በ፳፻ወ፲ ዓም ተሻሽሎ የወጣየኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያንሕገ

ቤተ ክርስቲያን" ተብሎ ሊጠቀስ ይችላል፡፡

## አንቀጽ ፪
## ትርጓሜ

የቃሉ አገባብ ሌላ ትርጉም የሚያሰጠው ካልሆነ በቀር በዚህ ሕግ ውስጥ፣

፩ "ቤተ ክርስቲያን" ማለት ክርስቶስን በተዋሕዶ አንድ አካል፣ አንድ ባሕርይ፣ ብላ የምታምን ጥንታዊት፣ሐዋርያዊት፣ በሁሉም ያለች፣ አንዲትና ቅድስት የሆነችው የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ማለት ነው፡፡

፪ "ቅዱስ ሲኖዶስ" ማለት ቅዱስ ፖትርያርክ፣ ሊቃነ ጳጳሳትና ኤጴስ ቆጶሳት የሚገኙበት ዓቢይ ጉባኤ ሆኖ ከፍተኛው የቤተ ክርስቲያኒቱ መንፈሳዊና አስተዳደራዊ ሕግ አውጭና ወሳኝ አካል ነው፡፡

፫ "የቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባኤ" ማለት መላው የቅዱስ ሲኖዶስ አባላት የሚገኙበት ጉባኤ ነው፡፡

፬ "ፓትርያርክ"ማለት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ርእሰ አበው፤ አበብዙኃን ማለት ነው፡፡

፭ "ሊቀ ጳጳስ" ማለት በኤጴስ ቆጶስነት (በጳጳስነት) ሲያገለግል ከቆየ በኋላ በቅዱስ ሲኖዶስ ፈቃድ በቅዱስ ፓትርያርኩ ፊርማ በሊቀ ጳጳስነት መዓርግ የሚሠየም የቤተ ክርስቲያን አባት ነው፡፡

፮ "ኤጲስ ቆጶስ" ወይም ‹‹ጳጳስ›› ማለት በድንግልና መንኩሶ ቤተ ክርስቲያንን በዲቁናና በክህነት እንዲሁም በቁምስና ሲያገለግል ቆይቶ የኤጴስ ቆጶስነትን መዓርግ የተቀበለ የቤተ ክርስቲያን ኖላዊ ወይም ጠባቂ ማለት ነው፡፡

፯. ‹‹የቅዱስ ሲኖዶስ ጽ/ቤት›› ማለት በቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባኤና በቋሚ ሲኖዶስ የሚወሰኑ ውሳኔዎችን እየተከታተለ የሚያስፈጽም ጽ/ቤት ነው ፡፡

፰. "ቋሚ ሲኖዶስ" ማለት ፓትርያርክ፣ የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ፣ ጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ እንዲሁም ከቅዱስ ሲኖዶስ አባላት መካከል ዐራት ሊቃነ ጳጳሳት ወይም ኤጴስ ቆጶሳት (ጳጳሳት) በአባልነት፣ የሚገኙበት ጉባኤ ነው፡፡
፱. "ጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት" ማለት የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ነው፡፡

፲. "ጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ" ማለት በቅዱስ ሲኖዶስ ተመርጦ በፖትርያርኩ በሚፈረም ደብዳቤ የተሠየመ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ዋና የሥራ መሪ ነው፡፡

፲፩. "አስተዳደር" ማለት በቤተ ክርስቲያኒቱ መዋቅር ከጠቅላይ ቤተ ክህነት እስከ አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን ያለውንና የድርጅቶችን አስተዳደርና አመራር የሚያጠቃልል የአስተዳደር ሥራ ነው፡፡

፲፪."የአስተዳደር ጉባኤ" ማለት በዋና ሥራ አስኪያጅ የሚመራ የመምሪያና የድርጅት ኃላፊዎች የሚገኙበት ስብሰባ ነው፡፡

፲፫. "መምሪያ" ማለት በጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት የሚገኝ ዓቢይ የሥራ ዘርፍ ነው፤

፲፬. "ሀገረ ስብከት" ማለት በቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔ ተለይቶ የተከለለና በሊቀ ጳጳስ ወይም በኤጴስ ቆጶስ የሚመራ የቤተ ክርስቲያን መንፈሳዊና አስተዳደራዊ ክልል ነው፡፡

፲፫. "ድርጅት" ማለት በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ሥር የተቋቋመና የሚቋቋም ድርጅት ነው፡፡

፲፬. "ሥራ አስኪያጅ" ማለት በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን የመሥሪያ ቤቶች ሥራ መሪ ነው፡፡

፲፭. "ሠራተኛ" ማለት በቤተ ክርስቲያኒቱ መሥሪያ ቤቶች በቋሚነት ወይም በጊዜያዊነት ተመድቦ (ተቀጥሮ) መንፈሳዊ፣ አስተዳደራዊ ወይም ሌላ ዓይነት አገልግሎት የሚያበረክት ሰው ነው፡፡

፲፮. "አገልጋይ" ማለት በቅዳሴ ወይም በማኅሌት ወይም በሌላ መንፈሳዊ ግልጋሎት በቤተክርስቲያን ውስጥ በቋሚነት ወይም በጊዜያዊነት ተመድቦበክፍያ ወይም በነፃ መንፈሳዊ ግልጋሎት የሚሰጥ ማንኛውም ሰው ማለት ነው

፲፱. "ዲያቆን" ማለት በቤተ ክርስቲያን ቀኖና መሠረት የተሠየመ ላእከ ካህን ነው፡፡

፳. "ቄስ" ማለት በኤጴስ ቆጶስ አንብሮተ እድ (እጅ በመጫን) መንፈሳዊ ሥልጣን የተሰጠውና በቤተመቅደስ በቅዳሴ፤ በውዳሴ፤ በዝማሬና በሰዓታት ቤተ ክርስቲያንን የሚያገለግል ባራኪ፤ ቀዳሽና ናዛዥ የንሥሐ አባት ማለት ነው፡፡

፳፩. "ቆሞስ" ማለት ከኤጴስ ቆጶስ በታች ሆኖ የመባረክና ምንኩስናን የመስጠት ሥልጣን ያለው ቤተ ክርስቲያንን በምንኩስና የሚያገለግል ካህን ነው፡፡

፳፪ "ምእመን" ማለት በቤተ ክርስቲያን ቀኖና መሠረት ተጠምቆ የቤተ ክርስቲያኒቱ አባል የሆነ አማኝ ማለት ነው፡፡

፳፫. "መነኩሴ" ማለት በራሱ ፈቃድ ዓለማዊ ግብርን ሁሉ መንኖ(ትቶ) እንደ ሞተ ሰው ተገንዞ ጸሎተ ፍትሐት የደረሰለት፤ የተጸለየበትና የተባረከን ቆብ የጫነ ካህን ወይም ምእመን ማለት ነው።

፳፬. "ገዳም" ማለት የመነኮሳት በዓት (መኖሪያ) የሆነ ከዓለማዊ መንደር የራቀ ታላቅ ቤተ ክርስቲያን ነው።

፳፭. ‹‹ደብር›› ማለት የተሟላ አገልግሎት የሚፈጽምበትና በቅዱስ ፓትርያርክ ወይም በሊቀ ጳጳስ ደብር የሚል መዓርግ የተሰጠው ቤተ ክርስቲያን ነው ።

፳፮. ገጠር ቤተ ክርስቲያን ማለት ምሥጢራተ ቤተ ክርስቲያን በተሟላ ሁኔታ የሚሰጡበት ሆኖ ደብር የሚል መዓርግ ያልተሰጠው ቤተ ክርስቲያን ነው ።

፳፯. "አበምኔት" ማለት የወንዶች ገዳም አስተዳዳሪ ወይም አባት ማለት ነው።

፳፰. "እመምኔት" ማለት የሴቶች ገዳም አስተዳዳሪ ወይም እናት ማለት ነው።

፳፱. አስተዳዳሪ ማለት

ሀ. የገዳም መምህር (አበ ምኔት/እመምኔት)
ለ. የደብር አለቃ
ሐ. ለገጠር ቤተ ክርስቲያን ዋና ኃላፊ ሆኖ የተሠየመ ቄስ ገበዝ ወይም መሪጌታ ማለት ነው ።

## አንቀጽ ፫
## የቤተ ክርስቲያን ሥያሜ

ቤተክርስቲያኒቷ "የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን" በመባል ትጠራለች ።

## አንቀጽ ፬
## የቤተ ክርስቲያን ዓርማ

### ፩. የዓርማው ቅርጽና ይዘት፡-

፩.፩. መደቡ ነጭ፤
፩.፪. ዙሪያው የስንዴ ዛላና የወይን ዘለላ፤
፩.፫. ከላይ ከአናቱ አክሊል፤ ከታች ከግርጌው መሐል ለመሐል ወጥቶ አናቱ ከአክሊሉ ሥር የደረሰና መስቀል ያለበት አርዌ ብርት፤
፩.፬. በግራ ሁኖ በቀኝ እጁ አርዌ ብርት፤ በግራ እጁ ዘንባባ የያዘ መልአክ፤ በቀኝ ሁኖ በግራ እጁ አርዌ ብርት በቀኝ እጁ ዘንባባ የያዘ መልአክ፤
፩.፭. ከአርዌ ብርቱ ሥር ‹‹ነዋ ወንጌለመንግሥት›› ተብሎ የተጻፈበት ቅዱስ መጽሐፍ፤
፩.፮. ከቅዱስ መጽሐፍ ሥር መስቀልኛ የ‹‹ጳ›› ፊደል ቅርፅን የሚመስል፤ ሁለቱ ጫፎቹ ከመደቡ ወደ ውጭ የወጣ ሰበን፤
፩.፯. የስንዴ ዛላና የወይን ዘለላ በተገናኙበት የዓለም ምስል፤ ያለበት ይሆናል ።

### ፪. የዓርማው ትርጉም፡-

ሀ/ መደቡ ነጭ መሆኑ ዘመነ ሥጋዌ የምሕረት የደስታና የነፃነት ዘመን መሆኑን ያመለክታል፤ (ዮሐ. ፳፡፲፪፣ የሐ.ሥራ ፩፡፲)

ለ/ የዓርማው ዙሪያ በወይን ዛላና በስንዴ ዘለላ የተከበበ መሆኑ ምእመናን በቅዱስ ቁ¤ርባን አማካኝነት ከእግዚአብሔር ጋር አንድነትን ሥርየተ ኃጢአትን የዘለዓለም ሕይወትን የሚያገኙ መሆናቸውን ይገልፃል፤ (ዮሐ. ፮:፶፫-፶፰፣ ማቴ. ፳፮:፳፮-፳፱፣ መዝ. ፬:፯)

ሐ/ በዓርማው መሐል ቀጥ ብሎ የቆመ የዓርዌ ብርት ምስል በበላዩ ላይ መስቀል፣ ከዚያም ከፍ ብሎ አክሊለ ክህነት አለው፤ የዚህ ትርጉም ሕዝበ እስራኤል ዓርዌ ብርቱን ባዩ ጊዜ ከእባብ መርዝ እንደዳኑ ሁሉ በመስቀል ላይ በተሰቀለ በጌታችን በአምላካችንና በመድኃኒታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ያመኑ ሁሉ በዲያብሎስ ምክንያት ከመጣባቸው ፍዳ ኃጢአት የሚድኑ መሆናቸውን መስቀሉ የቤተ ክርስቲያን የድኅነት ዓርማ መሆኑን (ዘኁ. ፳፩:፰፣ ዮሐ. ፫:፲፬፣)
መ. አክሊል ቅዱሳን በሰማያዊ መንግሥት የሚቀዳጁትን አክሊለ ክብርና ማኅተመ ጽድቅን ይመለከታል፤ (ዘፀ. ፴፱:፴፣ ፩ተሰ. ፪:፲፱፣ ፪ጢሞ. ፬:፰፣ ፩ጴጥ. ፭:፲፬፣ ራዕ. ፪:፲፣ ፬:፲፬)

ሠ/ሁለት መላእክት የዘንባባ ዝንጣፊና ዓርዌ ብርቱን ይዘው ይታያሉ፤ ይህም ዘንባባ በመንፈስ ቅዱስ የሚገኝ መንፈሳዊ ደስታንና ድኅነተ ነፍስን ያመለክታል፤ ቅዱሳን መላእክት የቤተ ክርስቲያን ጠባቂዎችና የመልካም ዜና አብሳሪዎች መሆናቸውን ያሳያል፤ ዓርዌ ብርቱን ይዘው መቆማቸው ነገረ መስቀሉን አምኖና ሃይማኖቱን አጽንቶ ይዞ የሚኖር የዘለዓለም ድኅነትን የሚያገኝ መሆኑን ያመለክታል ። (መዝ. ፺:፲፩፣ ሉቃ.፲፫:፮-፱፣ ዕብ. ፩:፲፬)

ረ/ የዓርማው መሐል ቅዱስ መጽሐፍ ሆኖ ‹‹ነዋ ወንጌለ መንግሥት›› የሚል ጽሑፍ በበላዩ አለበት፣ የዚህ ትርጉም የቤተ ክርስቲያናችን ሃይማኖት፣ ትውፊትና፣ ቀኖና

በቅዱስ መጽሐፍ ትምህርት ላይ የተመሠረተ መሆኑን ያመለክታል፡ (ማቴ. ፳፬:፲፬)

ሰ/ ከቅዱስመጽሐፉ ግርጌ የሚታየው ሰበን ቅድስት ድንግል ማርያም ስታርግ ለቅዱስ ቶማስ ሐዋርያ የሰጠችውን ሰበን የሚገልፅ ሲሆን ትርጉሙ የቅድስት ድንግል ማርያም ትንሣኤንና ዕርገትን እንደዚሁም የምእመናን እናት መሆኗን የሚያመለክት ነው ። (ዮሐ. ፲፱:፳፯)

ሸ/ የስንዴው ዛላና የወይኑ ዘለላ በተገናኙበት ላይ የሚታየው ክብ ነገር ዓለምን የሚወክል ሆኖ ዓለም በክርስቶስ መዳኑን ያመለክታል ። (ዮሐ. ፫3:፲፯)

**<u>፫. የዓርማው ክብር:-</u>**

ሀ/ ዓርማው የቤተ ክርስቲያኒቱ ሉዓላዊ ክብር መገለጫና መለያ ስለሆነ በሀገር ውስጥም ሆነ በውጭ ሀገር የሚገኙ የቤተ ክርስቲኒቱ መዋቅር ጽ/ቤቶችን ከዚህ ዓርማ በቀር ሌላ ሊጠቀሙ አይችሉም ።

ለ/ የቤተ ክርስቲያኒቱ አካል ሆኖ ይህ ዓርማ የሌለበት ማኅተምና የማዘዣ ደብዳቤ የሚጠቀም ጽ/ቤት ማንኛውም የቤተ ክርስቲያኒቱ ጽ/ቤት ተቀባይነት አይኖረውም ።

## <u>አንቀጽ ፭</u>
## <u>ቋንቋ</u>

፩. አማርኛ የቤተክርስቲያኗ ማእከላዊ የአስተዳደር ሥራ ቋንቋ ይሆናል።
፪. ግዕዝ፣ አማርኛና የየአካባቢው ቋንቋ በጣምራ የቤተ ክርስቲያኗ የትምህርትና የአምልኮ ሥርዓት ማከናወኛ

ቋንቋ ሆነው ያገለግላሉ፡፡

## አንቀጽ ፮
## የተፈጻሚነት ወሰን

ይህ ሕግ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያንን እምነት፣ሥርዓት፣ትውፊት መሠረት አድርገው በየትኛውም የዓለም ክፍል በተቋቋሙና በሚቋቋሙ-ገዳማት፣ አድባራት፣ አጥቢያ አብያተ ክርስቲያናት፣ በየትኛውም ደረጃ ላይ በሚገኙ የቤተ ክርስቲያኗ አገልጋዮችና ሠራተኞች፣ ምእመናንና ምእመናት እንዲሁም በቤተክርስቲያኗ ሥር ልማትንና ዕድገትን ለማፋጠን በተቋቋሙና በሚቋቋሙ መንፈሳዊ፣ ኢኮኖሚያዊና ማኅበራዊ ተቋማት ላይ ተፈጻሚነት ይኖረዋል፡፡

## ምዕራፍ ሁለት
## የሕገ ቤተክርስቲያኗ መሠረታዊ መርሖዎች

## አንቀጽ ፯
## የሕገ ቤተ ክርስቲያን የበላይነት

፩. ይህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን የቤተ ክርስቲያኒቱ መንፈሳዊ፣ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ አስተዳደርን በሚመለከት የበላይ ሕግ ነው፡፡ ማንኛውም ሕግ፣ ልማዳዊ አሠራር፣ እንዲሁም በየትኛውም እርከን የሚገኝ የቤተ ክርስቲያኒቱ የአስተዳደር አካል ወይም ኃላፊ የሚሰጠው ውሳኔ ከዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን ጋር የሚቃረን ከሆነ ተፈጻሚነት አይኖረውም፡፡

፪. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን ባለሥልጣን፣ አገልጋይ ሠራተኛና ምእመን ይህን ሕገ ቤተ ክርስቲያን የማክበርና የማስከበር እንዲሁም ለሕጉ ተገዢ የመሆን ኃላፊነት አለበት፡፡

## አንቀጽ ፰
## ገለልተኛነት

፩. በኢትዮጵያ ፌደራላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፲፩ እንደተመለከተው ቤተ ክርስቲያን በመንግሥት ጉዳይ ጣልቃ አትገባም፡፡
፪. ቤተ ክርስቲያን ዘርን፣ ብሔርን፣ የፖለቲካ አመለካከትን፣ ቋንቋን፣ ሀብትንና የመሳሰሉትን መሠረት በማድረግ በአገልጋዮቿ እና በምእመኖቿ ላይ ልዩነት ሳታደርግ በእኩልነት ታገለግላለች፡

## አንቀጽ ፱
## የቤተ ክርስቲያን አቋም

፩. ቤተ ክርስቲያኒቱበኢትዮጵያ ፌዴራላዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፐብሊክ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፳፯ (፪)፣ እንዲሁም በ፲፱፻፶፪ ዓ.ም በወጣው የኢትዮጵያ ፍትሐ ብሔር ሕግ ቁጥር ፫፻፺፰ እና ፫፻፺፱ እና አግባብ ባላቸው ሌሎች ሕግጋት በተደነገገው መሠረት በየደረጃው ባሉት መሥሪያ ቤቶቿ አማካኝነት በአስተዳደር ሕጎች የተፈቀዱትን መብቶች ሁሉ ትሠራባቸዋለች፣ ውል ለመዋዋል፣ ለመክሰስ፣ ለመከሰስ፣ የንብረት ባለቤት ለመሆን፣ ውርስና ልዩ ልዩ ስጦታዎች ለመቀበልና ሌሎችም ሕጋዊ ውጤቶች ያሉዋቸውን ተግባራት ለማከናወን ትችላለች፡፡

፪. ከኢትዮጵያ ውጭ ባሉት ሀገሮች የሚገኙ አህጉረ ስብከት፣ የአጥቢያ አብያተ ክርስቲያናትና ሌሎች የቤተ ክርስቲያኒቱ አካላት በሚገኙባቸው ሀገሮች ሕግጋት መሠረት ዕውቅና አግኝተው አገልግሎታቸውን ያካሒዳሉ፡፡

፫. ቅዱስ ሲኖዶስ በሚሠይመው የሀገረ ስብከት ሊቀ ጳጳስ የማይመራ የአጥቢያ ቤተ ክርስቲያን አስተዳደር ተቀባይነት የለውም ፡፡

፬. ቤተ ክርስቲያኒቱ በምታስተዳድራቸው ካህናትና ምእመናን ላይ ባላት የዳኝነት ሥልጣን መሠረት፤

ሀ/ በቤተ ክርስቲያኒቱ አስተዳደር ውስጥ ለሚፈጸሙ የሥራ ጉድለቶች በቤተ ክርስቲያኒቱ ሕግና ሥርዓት መሠረት የመቆጣጠር፣ የመቅጣት፣ የማረም፣ ከሥራ የማሰናበት በጡረታ የማግለል ወዘተ... ሥልጣን አላት፤ በሂደት ዝርዝር ሕግ ይወጣል።

ለ/ የቤተ ክርስቲያኒቱ አስተዳደራዊ ዳኝነት እንደክሱ አቀራረብ እየተመዘነ የሚታየው፣

1. በሥነ ሥርዓት (በዲስፒሊን) ጉባኤ
2. በአስተዳደር ጉባኤ
3. በመንፈሳዊ ፍ/ቤት
4. በቋሚ ሲኖዶስ
5. በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ነው።

ሐ/ በቅዱስ ሲኖዶስ የሚወሰኑ ውሳኔዎች የመጨረሻ ውሳኔዎችይሆናሉ።

መ/ በየደረጃው ያሉት የዳኝነት አካላት የሥልጣን ድንበርከቤተ ክርስቲያኒቱ በሚወጡ ሕጎችና ደንቦች ይወሰናል።

ሠ/ ወንጀል ነክ ከሆኑ ጉዳዮች ውጪ ካህናት፣ ኤጲስ ቆጶሳትና ሊቃነ ጳጳሳት መንፈሳዊ ሥራቸውን (አገልግሎታቸውን) በሚመለከት ቢከሰሱወይም ቢከሱጉዳያቸው በቤተ ክርስቲያን ሕግና የዳኝነት ሥርዓት ይታያል እንጂ በመደበኛ ፍርድ ቤቶች አይዳኙም።

፭. ቤተ ክርስቲያንለመንፈሳዊ አገልግሎት የምትጠቀምባቸውን ምርቶችና ንዋያተ ቅድሳት በአጠቃላይ

ማምረትና ማሠራጨት ትችላለች፡፡

፮. የመንግሥት ሕግጋት እንደተጠበቁ ሆነውቤተ ክርስቲያን ከጥንት ጀምሮ በሊቃውንት ልጆቿ አማካኝነት እየጻፈችና እያዘጋጀች ስትጠቀምባቸው፣ ስታስተምርባቸውና ስትጠብቃቸው የኖሩትንና በየገዳማቱ፣ በየአድባራቱና በየገጠር አብያተ ክርስቲያናቱ የሚገኙትን ቅዱሳት መጻሕፍትና ልዩ ልዩ ቅርሶች በባለቤትነት የመጠበቅና የማስጠበቅ መብት አላት፡፡

፯.ቤተ ክርስቲያን ያሏትን ጥንታውያን መጻሕፍት እየተረጐመችና እያሳተመች ለምእመናን አገልግሎት የማዋልና የማሰራጨት እንዲሁም የጥናትና የምርምር ተቋማትን የማቋቋም መብት አላት፡፡

፰. ሀ. ቤተ ክርስቲያን የምግባረ ሠናይ ድርጅቶችን (የበጎ አድራጎት ድርጅቶችን) የመመሥረት፣

ለ. ማሠልጠኛዎችንና መንፈሳዊ ትምህርት ቤቶችን የማቋቋም፣ ለተቋቋሙትም እስከ ኮሌጅና ዩኒቨርሲቲ ደረጃ ማሳደግናዕውቅና የመስጠት፣ በትምህርት ቤቶቿም አማካኝነት ሃይማኖቷንና ቀኖናዋን የማስተማርና የማስፋፋት፣ የማጠናከርና የምስክር ወረቀት የመስጠት መብት አላት፡፡

፱. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ከቅዱስ ሲኖዶስ አባላት ጀምሮ የካህናት፣ የምእመናንና የሰንበት ትምህርት ቤት ተወካዮች የሚገኙበትና በዓመት አንድ ጊዜ የሚደረግ አንድ አጠቃላይ ሰበካ መንፈሳዊ ጉባኤ ይኖረዋል። በዚህም ጉባኤ ጠቅላላ የቤተ ክርስቲያኒቱ የሥራ ሒደት

የሚገመገምበትና አስተዳደራዊውም ሆነ መንፈሳዊው ጉዳይ ሁሉ ውሳኔ የሚሰጥበት ይሆናል ።

## አንቀጽ ፲
## የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን የሥልጣን መዋቅር

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ከቅዱስ ሲኖዶስ እስከ አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን የተዘረጋ ከላይ ወደታች የሚወርድ መዋቅር ያላት ሲሆን ይህም የሚከተለው ነው፡፡

፩. ቅዱስ ሲኖዶስ
፪. ፓትርያርክ
፫. ቋሚ ሲኖዶስ
፬. የቅዱስ ሲኖዶስ ጽሕፈት ቤት
፭. ጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት
፮. የሀገረ ስብከት ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት
፯. የወረዳ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት
፰. የአጥቢያ ቤተ ክርስቲያን ሰበካ ጉባኤ ጽሕፈት ቤት

## አንቀጽ ፲፩
## የመልካም አስተዳደር መርሖዎች

የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር በዋነኛነት በሚከተሉት የመልካም አስተዳደር መርሐዎች ይመራል፤
፩. መንፈሳዊነት
፪. ፍትሐዊነት
፫. ሕጋዊነት

፬. አሳታፊነት
፭. ግልጸኛነት
፮. ተጠያቂነት
፯. ተደራሽነት
፰. ምላሽ ሰጪነት
፱. ምሥጢር ጠባቂነት
፲. ታማኝነት

## አንቀጽ ፲፪
## የሠራተኞች መሠረታዊ መብቶችና ግዴታዎች

፩. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አገልጋይ በቤተ ክርስቲያኒቷ ሕግ ፊት እኩል ሆኖ የመታየት መብት አለው።

፪. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አባል ደረጃው በሚፈቅድለት መጠን በቤተ ክርስቲያኗ ውስጥ በሚደረጉ መንፈሳዊ፣ ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ እንቅስቃሴዎች ውስጥ የመሳተፍ መብት አለው ።

፫. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አባል ለደረሰበት አስተዳደራዊ በደል ቅሬታ የማቅረብ፣ ለቀረበበት ቅሬታ ለአቀረበው ቅሬታም ዳኝነት የማግኘት መብት አለው ።

፬. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አባል የቤተ ክርስቲያን ዓቅም በፈቀደ መጠን መንፈሳዊ ዕውቀቱን፣ ለማጎልበት የሚረዱ ትምህርትና ሥልጠና የማግኘት መብት አለው ።
፭. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን ሠራተኛና አገልጋይ ወደፊት በሚወጣ የአስተዳደር ደንብ በሚወሰነው መሠረት ሳምንታዊና ዓመታዊ ዕረፍትን የማግኘት መብት አለው ።

፮. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አባልበዘር፣ በብሔር፣ በቀለም፣ በሀብት ወይም በሌሎች ከሚፈጸም አድሎአዊ

አሠራር የመጠበቅ መብት አለው፡፡

፯. ከኤጲስ ቆጶሳት፣ ጳጳሳትና ሊቃነ ጳጳሳት በቀር በየትኛውም ደረጃ ላይ የሚገኙ የቤተ ክርስቲያን አገልጋዮችና ሠራተኞች ዕድሜያቸው ለጡረታ ሲደርስ ጡረታ የማግኘት መብት አላቸው ፡፡ የጡረታ መውጫ ዕድሜና የጡረታ አስተዳደርን በሚመለከት ቅዱስ ሲኖዶስ ዝርዝር ደንብ ያወጣል ፡፡

፰. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አባል ከቤተ ክርስቲያኒቷ የሥራ ጠባይ አንፃር የተጓደለበትን መብት ሥርዓቱን ጠብቆ ከመጠየቅ በቀር የሥራ ማቆም አድማ ማድረግ ወይም እንዲደረግ ማነሣሣት አይችልም፡፡ ድርጊቱ በአስተዳደርና ሃይማኖታዊ ቀኖና የሚያስጠይቅ ተግባር ሆኖ እንደ ጥፋቱ ክብደት ከሥራና ከሥልጣነ ክህነት የሚያሳግድ ሊሆን ይችላል፡፡

፱. ማንኛውም አገልጋይና ሠራተኛ በተቀጠረበት የሥራ መደብ ሥራውን ራሱ የመሥራት ግዴታ አለበት፡፡

፲. ማንኛውም አገልጋይና ሠራተኛ ለተመደበበት አገልግሎትና ሥራብቁ በሆነ የአእምሮና የአካል ጥንካሬ ዝግጁ ሆኖ መገኘት አለበት፡፡

፲፩. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አባል በቤተ ክርስቲያኒቱ የአስተዳደር አካላት የሚተላለፉትን ሕጎች፣ ደንቦች፣ መመሪያዎች፣ ትእዛዞች እና ውሳኔዎች ማክበር አለበት፡፡

፲፪. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያንአገልጋይና ሠራተኛ ራሱን ከሙስናዊ አሠራር ነፃ በማድረግ ቤተ ክርስቲያንን እና ምእመናንን በመንፈሳዊነት፣ በቅንነትና በታማኝነት ማገልገል አለበት፡፡

፲፫. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያን አገልጋይና ሠራተኛ በሕጋዊ ውሳኔ ካልታገደና ካልተሰናበተ በቀር ሠርቶ ደመወዝ የማግኘት መብቱ በሕግ የጠበቀ ነው ፡፡

፲፬. የቤተ ክርስቲያን አባላት፣አገልጋዮችና ሠራተኞች መብትና ግዴታ እንዲሁም ሥነ-ምግባርን የሚመለከቱ ዝርዝር ደንቦች ይወጣሉ፡፡

## አንቀጽ ፲፫
## የምእመናን መሠረታዊ መብቶችና ግዴታዎች

፩. ምእመናን በቤተ ክርስቲያኒቷ ውስጥ የሚሰጡ መንፈሳዊ፣ ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ ግልጋሎቶችን ደረጃቸው (ዓቅማቸው) በሚፈቅደው መሠረት በእኩልነትና ያለአድልዎ የማግኘትና የመጠቀም መብት አላቸው፡፡

፪. በአጥቢያ ቤተ ክርስቲያንሰበካ ጉባኤ ሥር በልማት በምግባረ ሠናይና በመንፈሳዊ አገልግሎት ድጋፍ ሰጭነት የመሣተፍ መብት አላቸው፡፡

፫. የመመዘኛ መስፈርቱን አሟልተው ሲገኙ ለሰበካ ጉባኤ አስተዳዳርየመመረጥና የመምረጥ መብት አላቸው፡፡

፬. በቅዱስ ሲኖዶስ የሚወጡ መንፈሳዊ፣ ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ ሕጎችን፣ ደንቦችንና ውሳኔዎችን የማክበርና የማስከበር ግዴታ አለባቸው፡፡

# ምዕራፍ ሦስት
# የቤተ ክርስቲያኒቱ የአስተዳደር ሥልጣን አወቃቀርና ክፍፍል

## ክፍል አንድ
## ቅዱስ ሲኖዶስ
## አንቀጽ ፲፩
## የቅዱስ ሲኖዶስ ልዕልና

፩. በመንፈስ ቅዱስ የሚመራው ቅዱስ ሲኖዶስ የመንበረ ሐዋርያት ወራሽ ስለሆነ በቤተ ክርስቲያኒቱ የመጨረሻው ከፍተኛ የሥልጣን ባለቤት ነው፡፡

፪. ቅዱስ ሲኖዶስ ከማንኛውም የቤተ ክርስቲያኒቱ የሥልጣን መዋቅር ሁሉ የበላይ አካል ስለሆነ ቤተ ክርስቲያንን የመጠበቅ፤ የመምራት፤ ሕጎችን፤ ልዩ ልዩ ደንቦችንና መመሪያዎችን የማውጣትና የመወሰን ሥልጣን አለው፡፡

፫. ቅዱስ ሲኖዶስ በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ ፪ በተገለጸው አጠቃላይ አነጋገር ሳይወሰን፤

ሀ. ሃይማኖትንና ቀኖና ቤተ ክርስቲያንን አስመልክቶ የቤተ ክርስቲያኒቱ ከፍተኛው የሥልጣን አካል በመሆኑ በሃይማኖት፣ በቀኖና፣ በመንፈሳዊ ትውፊትና ባህል ጉዳዮች ላይ መልስ ይሰጣል፣ የእምነቱን መሠረታዊ ጉዳዮች የሚመለከቱ መጻሕፍት እንዲጻፉና፣ ትርጉም እንዲሰጥባቸው፣ ያደርጋል፡፡

ለ. በቤተ ክርስቲያን የበዐላትን አከባበርና አጽዋማትን አስመልክቶ በሚነሡ ጉዳዮች ላይ የመጨረሻ ውሳኔ ይሰጣል፡፡

## አንቀጽ ፲፩
## የቅዱስ ሲኖዶስ ዓላማዎች

ቅዱስ ሲኖዶስ የሚከተሉት ዓላማዎች ይኖሩታል፡፡

፩. የቅድስት ቤተ ክርስቲያን ሃይማኖታዊ፣ ቀኖናዊና ታሪካዊ ትውፊት እንዳይፋለስ መጠበቅና ማስጠበቅ፣ አገልግሎቷም የተሟላ እንዲሆን ማድረግ፤

፪. ጥንታውያን የቤተ ክርስቲያን ትምህርት ቤቶችን መጠበቅና ማስፋፋት፤

፫. ገዳማትንና ሥርዓተ ገዳማትን እንደዚሁም ሥርዓተ ምንኩስናን መጠበቅና ማስጠበቅ፤

፬. የሥርዓተ ክህነት አሰጣጥና አጠባበቅ በፍትሐ መንፈሳዊ በተደነገገው መሠረት እንዲፈጸም ክትትልና ቁጥጥር ማድረግ

፭. ስብከተ ወንጌልን በማስፋፋትና በማጠናከር፤ በሀገር ውስጥና በውጭ ሀገር ምእመናንን ማብዛትና መጠበቅ፤

፮. ምእመናን በተለይም ወጣቶች ከአበው የተቀበሉትን ሃይማኖት፣ ቀኖና፣ ትውፊትና ባህል ጠብቀው፣ በትምህርትና በሥነ-ምግባር ታንፀው፣ እንዲያድጉ የሰንበት ትምህርት ቤቶችንና ዘመናውያን ትምህርት ቤቶችን በከፍተኛ ደረጃ ማጠናከርና ማስፋፋት፤

፯. የሰው ዘር ሁሉ ከረሀብ፣ ከእርዛት፣ ከበሽታና ከድንቁርና ተላቆ በሰላምና በአንድነት በመተሳሰብና በመረዳዳት በመንፈሳዊ ሕይወት እንዲኖር ማስተማርና መጸለይ፤

፰. ቤተ ክርስቲያን የልማት ሥራ የምታከናውንባቸው ፖሊሲዎችንና ስትራቴጂዎችን በማውጣት በኢኮኖሚ ራሷን እንድትችል ሁኔታዎችን ማመቻቸት፤

፱. በቤተ ክርስቲያኒቱ ውስጥ ፍትሕ ርትዕ እንዲሰፍን የሁሉም መብት በሕግ ፊት እንዲከበር እኩልነትና አንድነት እንዲረጋገጥ ጠንክሮ መሥራት፤

፲. የቤተ ክርስቲያኒቱን አንድነት ማስጠበቅና ማስከበር፤
፲፩. ማንኛውንም የቤተ ክርስቲያኒቱን ሀብት ማስጠበቅ፣ መጠበቅና መቆጣጠር፤

## አንቀጽ ፲፮
## የቅዱስ ሲኖዶስ አካላት

ቅዱስ ሲኖዶስ በአንቀጽ ፲፮ የተመለከቱትን ዓላማዎች ለማስፈጸም የሚያግዙ የሚከተሉት አካላት ይኖሩታል።

፩. የቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባኤ
፪. የቅዱስ ሲኖዶስ ጽቤት
፫. ቋሚ ሲኖዶስ
፬. ተጠሪነታቸው ለቅዱስ ሲኖዶስ የሆኑ መምሪያዎች (የሥራ ክፍሎች) ይኖሩታል።

## አንቀጽ ፲፯
## የቅዱስ ሲኖዶስ ተግባርና ኃላፊነት

ቅዱስ ሲኖዶስ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል።
፩. ቤተ ክርስቲያንን በበላይነት ይመራል፤ ይጠብቃል።
፪. ፍትሕ መንፈሳዊ በሚፈቅደው መሠረት ሕጎችን፣ ደንቦችንና ልዩ ልዩ መመሪያዎችን ያወጣል፣ ያሻሽላል፣ ይሽራል።

፫. የቤተ ክርስቲያኒቱን አጠቃላይ የምጣኔ ሀብትና የሙዓለ ንዋይ አስተዳደር መመሪያዎችን (ፖሊሲዎችን) ያወጣል። ፬.ዓመታዊውን የቤተ ክርስቲያን በጀት ያጸድቃል፤ ተግባራዊነቱንም ይቆጣጠራል።

፭. የቤተ ክርስቲያኒቱን አስተዳደራዊ መዋቅር እንዲሁም የጽሕፈት ቤቶችን ደረጃና ተጠሪነት ይወስናል።

፮. የቤተ ክርስቲያኒቱ አስተዳደርና አገልግሎት በቀኖና ቤተ ክርስቲያን መሠረት እንዲመራ ያደርጋል።

፯. የቤተ ክርስቲያኒቱን እምነት በሀገር ውስጥና በውጭ ሀገር በማስፋፋት ምእመናን እንዲበዙ ያደርጋል፤

፰. መንፈሳዊና ዘመናዊ ትምህርት ቤቶችን አቅም በፈቀደ መጠን በየአካባቢው ያቋቁማል ያስፋፋል።

፱. የክርስቶስን ወንጌል መንግሥትና ቀኖና ቤተ ክርስቲያንን ያስተምራል ያስፋፋል። በሀገር ውስጥም ሆነ በውጭ ሀገር አዲስ መንበረ ጵጵስናና የሀገረ ስብከት ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤቶችን እንደ አስፈላጊነቱ ያቋቁማል።

፲. ቤተ ክርስቲያን ከውጭ አኃት አብያተ ክርስቲያናት ጋር ያላትንና የሚኖራትን ግንኙነት ከሃይማኖትና ከቀኖና ቤተ ክርስቲያን አንጻር እየገመገመ ያስፋፋል ያጠናክራል።

፲፩. በውጭ ሀገራት በሚገኙ አህጉረ ስብከትና የአጥቢያ አብያተ ክርስቲያናት ለአገልግሎት ስለሚመደቡና እንደዚሁም በውጭ ሀገራት መንፈሳዊ ትምህርትን መከታተል ስለሚችሉ ካህናትና ሊቃውንተ ቤተ ክርስቲያን ምልመላና ምርጫ መሥፈርት ያወጣል።

፲፪. ቤተ ክርስቲያኒቱን ወክለው ለሥራ፣ ለስብሰባም ሆነ ለጥናት ወደ ውጭ ሀገራት ስለሚላኩ ተወካዮች አመራረጥ መመሪያ ያወጣል፡፡

፲፫. በቋሚ ሲኖዶስ የሚያገለግሉ ጳጳሳትን በየሦስት ወሩ እየመደበ እንዲሠሩ ያደርጋል፡፡

፲፬. የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ እንደዚሁም ጠቅላይ ሥራ አስኪያጁን፣ በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን መሠረት የሚቋቋሙትንና ተጠሪነታቸው ለቅዱስ ሲኖዶስ የሆኑ አባላትን ይመርጣል፣ የቤተ ክርስቲያን የልማት፣ የምግባረ ሠናይና የበጎ አድራጎት ድርጅቶችን የቦርድ አባላትን እና ኃላፊዎችን መርጦ ይሰይማል፣

፲፭. ቅዱስ ሲኖዶስ በየጊዜው በሚያደርጋቸው ስብሰባዎች የሚቀርቡትን አጀንዳዎች ያጸድቃል፤ እንደ አስፈላጊነቱም ያሻሽላል፡፡

፲፮. የቤተ ክርስቲያን ጉዳዮችን በተመለከተ ለጥፋተኞችና ለበደለኞች እንደ ጥፋታቸው መጠን ምሕረትን ይሰጣል፣ ይቅርታንም ያደርጋል፤ አስፈላጊም ከሆነ በቀኖና ይቀጣል፡፡

፲፯. የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤትና በሥሩ ያሉ መምሪያዎችና አህጉረ ስብከት እንደዚሁም ሌሎች ተጠሪነታቸው ለቅዱስ ሲኖዶሱ የሆኑ አካላት የሥራና የሒሳብ እንቅስቃሴ በየዓመቱ ያስመረምራል፤ እንደአስፈላጊነቱም በውጭ ኦዲተር እንዲመረመር ያደርጋል፤ የሚቀርበውንም የኦዲት ሪፖርት መርምሮ ተገቢውን ውሳኔ ይሰጣል፡፡
፲፰. በየደረጃው የሚገኙ መሥሪያ ቤቶች የሥራ እንቅስቃሴ የሚገመገምበትን ደንብ ያወጣል፡፡ቤተ ክርስቲያን በራሷም ሆነ በሌሎች የመገናኛ ብዙኃን ስለምትገለገልበት ሁኔታ ዝርዝር መመሪያ ያወጣል፡፡

፲፱. በቤተ ክርስቲያን ስም የሚሰበሰብ ነገር ግን ቅዱስ ሲኖዶስ በቀጥታ የማያውቀው፣ የማይቆጣጠረውና የማያዝበት ገንዘብና ማንኛውም ንብረት እንዳይኖር ጥብቅ ቁጥጥር ያደርጋል፤ ተግባራዊነቱንም ይከታተላል፤ በሕግም መብቱን ያስጠብቃል ።

፳. ቤተ ክርስቲያን በራሷም ሆነ በሌሎች የመገናኛ ብዙኃን ስለምትገለገልበት ሁኔታ ዝርዝር መመሪያ ያወጣል።

፳፩. የቤተ ክርስቲያን የልማት፣ የምግባረ ሠናይ ወይም የበጎ አድራጎት ድርጅቶችን ያቋቁማል።

፳፪. ጥንታውያን ገዳማትን ያጠናክራል፣ አዳዲስገዳማትን አድባራትንና የገጠር አብያተ ክርሲቲያናትንይመሠርታል፣ ሥርዓተ ገዳማትን የሚመለከት ደንብም ያወጣል።

፳፫. በቀኖና ቤተ ክርስቲያን መሠረት የንዋየ ቅድሳትን አዘገጃጀት፣ አጠቃቀምበተመለከተ ደንብ ያወጣል።

፳፬. በቤተ ክርስቲያኒቱ ውስጥ ታቅፈው መንፈሳዊ አገልግሎትን ለማበርከት ለተቋቋሙና ለሚቋቋሙ ማኅበራት እንደ አስፈላጊነቱ ዕውቅናን ይሰጣል፤ ማኅበራቱ በሰንበት ት/ቤቶች ማደራጃ መምሪያ ሥር እንዲደራጁ ያደርጋል። የማኅበራቱን መተዳደሪያ ደንብም መርምሮ ያጸድቃል፣ ያሻሽላል፣ አስፈላጊ ሆኖ ሲያገኘውም ማኅበራቱን ያግዳል ይሠርዛል።

በዚህ አንቀጽ ንኡስ ቁጥር ፲፱ ላይ በተቀመጠው መሠረት የማኅበራቱ ገንዘብና ንብረት በቤተ ክርስቲያኒቱ ሞዴላሞዴል እንዲሰበሰብ ያደርጋል፣ የማኅበራቱን ገንዘብ፣ ንብረትና አስተዳደር ይቆጣጠራል፣ ኦዲት ያደርጋል፣ የማስተካከያ እርምትም ይወስዳል። ማኅበራቱ በቤተ ክርስቲያኒቱ አስተዳደር ጣልቃ እንዳይገቡ ይቆጣጠራል፣ ስለ ማኅበራቱ

አስተዳደርና ቁጥጥር ዝርዝር ደንብ ያወጣል።

፳፫. በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን አንቀጽ ፱ (፱) የተጠቀሰው አጠቃላይ ሰበካ መንፈሳዊ ጉባኤ የሚሰጠውን ውሳኔ እንደገና ገምግሞና አጣርቶ ተገቢውን መመሪያና ውሳኔ ይሰጣል ።
ቤተ ክርስቲያንንና የቤተ ክርስቲያን ጉዳዮችን በተመለከተ ቅዱስ ሲኖዶስ የሚሰጠው ውሳኔ የመጨረሻ ይሆናል።

፳፬. በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን ባልተካተቱ ሌሎች የቤተ ክርስቲያን ጉዳዮች ላይ የመወሰን ሙሉ ሥልጣን ይኖረዋል።

## አንቀጽ ፲፰
## የቅዱስ ሲኖዶስ አባላት

፩. በቀኖና ቤተ ክርስቲያንና በፍትሐ መንፈሳዊ አንቀጽ ፬ እና ፫ መሠረት ቅዱስፓትርያርክ፣ በቤተ ክርስቲያኒቱ አህጉረ ስብከትና በልዩ ልዩ የሥራ ክፍሎች የተሾሙ ሊቃነ ጳጳሳትና ኤጴስ ቆጶሳት (ጳጳሳት) ሁሉ የቅዱስ ሲኖዶስ አባላት ናቸው።

፪. የቅዱስ ሲኖዶስ አባልነት ዕድሜ ልክ ይሆናል።

፫. ከቅዱስ ፓትርያርክ ጀምሮ እያንዳንዱ ሊቀ ጳጳስና ኤጴስ ቆጶስ (ጳጳስ) ተጠሪነቱ ለቅዱስ ሲኖዶስ ነው።

፬. በዚህ አንቀጽ ንኡስ አንቀጽ ፪ የተደነገገው እንደተጠበቀ ሆኖ አንድ የቅዱስ ሲኖዶስ አባል በሕመም ወይም በእርግና ወይም በሌላ ከዓቅሙ በላይ በሆነ ምክንያት የቅዱስ ሲኖዶስ ጉባዔያትን መካፈል ካልቻለ ከሥራ መደቡ ተነሥቶ ሙሉ ጥቅሙ ተከብሮለት ቤተ ክርስቲያኒቱ ባዘጋጀችው የማረፊያ ቦታ በክብር ይቀመጣል።

፰. አንድ የቅዱስ ሲኖዶስ አባል ኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ሃይማኖትንና ቀኖና ቤተ ክርስቲያንን የሚያፋልስ ሆኖ ከተገኘ ከአባልነቱ ይሠረዛል፡፡ ይህም የሚሆነው በቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔ ከተሰጠ በኂላ ነው፡፡

፱. በሃይማኖትም ሆነ በቀኖና ቤተ ክርስቲያን የተከሰሰ የሲኖዶስ አባል በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ቀርቦ ራሱን የመከላከል መብቱ የተጠበቀ ነው፡፡

፲. አንድ የቅዱስ ሲኖዶስ አባል ስለራሱ ጉዳይ በሚታይበት ስብሰባ ላይ በአባልነት መገኘት አይችልም፡፡

## አንቀጽ ፲፬
## የቅዱስ ሲኖዶስ የስብሰባ ሥርዓት

፩. ፍትሐ መንፈሳዊ በአንቀጽ ፭ ቁጥር ፻፷፬ በሚያገዘው መሠረት ቅዱስ ሲኖዶስ በዓመት ሁለት ጊዜያት መደበኛ ስብሰባን ያካሒዳል፡፡ የስብሰባውም ጊዜ፤

ሀ/ የመጀመሪያው ጉባኤ በየዓመቱ ጥቅምት ፲፪ ቀን
ለ/ የሁለተኛው ጉባኤ ትንሣኤ በዋለ በሃያ አምስተኛው ቀን /በርክበ ካህናት/ የሚካሒደው ነው፡፡

፪.የቅዱስ ሲኖዶስ ስብሰባ ከመካሔዱ ቢያንስ ከሁለት ሳምንታት በፊት የስብሰባውን ዕለት፣ የስብሰባውን ሥፍራ የሚገልፅ ደብዳቤ ለእያንዳንዱ የቅዱስ ሲኖዶስ አባል እንዲደርስ ይደረጋል፡፡

፫. የቅዱስ ሲኖዶሱን ስብሰባ የሚጠራው ፓትርያርኩ፣ ወይም ስብሰባው የተጠራው በቋሚ ሲኖዶሱ ሲሆን የቅዱስ ሲኖዶሱ ዋና ጸሐፊ ነው፡፡

፬. አስቸኳይና ድንገተኛ ጉዳይ ሲያጋጥም፤

ሀ/ ቅዱስ ፓትርያርኩ ወይም ቋሚ ሲኖዶስ ወይም የቅዱስ ሲኖዶሱ ዋና ጸሐፊ በሚያደርጉት ጥሪ የቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ሊካሔድ ይችላል፡፡

ለ/ ከጠቅላላው አባላት ከግማሽ በላይ የሚሆኑ የቅዱስ ሲኖዶስ አባላት የቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ እንዲደረግ በጠየቁ ጊዜ ጥሪ ሊደረግና ስብሰባው ሊካሔድ ይችላል፡፡

፭. በሕመምና በሌሎች አጥጋቢ ወይም ከዓቅም በላይ በሆኑ ምክንያቶች ሁሉም የቅዱስ ሲኖዶስ አባላት በስብሰባው የማይገኙ ቢሆን፤

ሀ/ አስተዳደራዊ ጉዳዮችን ለሚመለከቱ አጀንዳዎች ከአባላት ከሦስት እጅ ሁለቱ እጅ ያህሉ ከተገኙ ምልዓተ ጉባኤ ይሆናል፤

ለ/ ሃይማኖትንና ቀኖና ቤተ ክርስቲያንን በሚመለከቱ ጉዳዮች ከአባላት ከዐራት እጅ ሦስቱ እጅ ከተገኙ ምልዓተ ጉባኤ ይሆናል፡፡

፮. ቅዱስ ሲኖዶስ በማናቸውም ስብሰባ ላይ ውሳኔዎችን ሲያሳልፍ፣

ሀ/ አስተዳደርን የሚመለከት ጉዳይ ከሆነ ከተገኙት አባላት መካከል ከግማሽ በላይ በሆነ ድምፅ የተደገፈው ሐሳብ ያልፋል፡፡

ለ/ አንድን ጉዳይ ለመወሰን የአባላቱ ድምፅ እኩል በእኩል ከሆነ ፓትርያርኩ ወይም ሰብሳቢው የደገፈው የውሳኔ ሐሳብ ያልፋል፡፡

ሐ/ሃይማኖትንና ቀኖና ቤተ ክርስቲያንን የሚመለከት ከሆነ በሙሉ ድምፅ ያልፋል፤ በሃይማኖትና በቀኖና ጉዳይ ድምፀ ተዓቅቦ ማድረግ አይቻልም፡፡ ቢገኝ ግን በአንቀጽ ፲፰ ንኡስ ቁጥር ፭ መሠረት ይፈጽማል

## አንቀጽ ፳
## የቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ርእሰ መንበር

፩. የቅዱስ ሲኖዶስ ስብሰባ በቅዱስ ፓትርያርክ ሰብሳቢነት ይመራል፡፡

፪. ከዚህ በታች በተመለከቱት ምክንያቶች ካልሆነ በቀር ቅዱስ ፓትርያርክ ርእሰ መንበር ያልሆነበት የቅዱስ ሲኖዶስ ስብሰባ ሊካሔድ አይችልም፡፡

ሀ/ ቅዱስ ፓትርያርኩ በዕርግና ወይም በጤና ችግር ወይም በሌላ አጥጋቢ በሆነ ምክንያት ለረጅም ጊዜ በሥራው ላይ የማይገኝበት ሁኔታ ተፈጥሮ ስብሰባውን መምራት ካልቻለ ስብሰባው የሹመት ቅድምና ካላቸው ሦስት አባላት መካከል በሚመረጠው አባት ሊመራ ይችላል፡፡

ለ/ ስብሰባው ፓትርያርኩን የሚመለከት ሲሆንም ሰብሳቢው በዚህ ንኡስ አንቀጽ ፊደል (ሀ) መሠረት ይሠየማል፡፡

## አንቀጽ ፳፩
## ስለ ቅዱስ ሲኖዶስ አባላት ሀብትና ንብረት

፩. አንድ የቅዱስ ሲኖዶስ አባል ከዚህ ዓለም በሞት በሚለይበት ጊዜ የግል የሆነ ገንዘብ ቢኖረው ይረዳቸው ለነበሩት ዕጓለ ማውታና ችግረኞች ይሰጣል፡፡( አብጥሊስ ፴፱)

፪. ኤጲስ ቆጶሱ መንፈሳዊ አገልግሎቱን ሲያከናውንባቸው የቆዩት መጻሕፍት፣ አልባሳት፣ አርዌብርት፣ መስቀሎች፣ መቋሚያዎችና የመሳሰሉት ሁሉ በቤተ ክርስቲያኒቱ ንብረት በስሙ ተመዝግበው በሀገረ ስብከቱ በሙዚየም ይቀመጣሉ፡፡

፫. ከዚህ በላይ የተደነገገው እንደተጠበቀ ሆኖ አንድ ሊቀ ጳጳስ ወይም ጳጳስ ወይም ኤጲስ ቆጶስ፦

ሀ/ ሲታመም ቤተ ክርስቲያኒቱ ታሳክመዋለች። ዝርዝር ጉዳዩ ቅዱስ ሲኖዶሱ በሚያወጣው ደንብ ይወሰናል።

ለ/ ባረፈም ጊዜ ዜና ዕረፍቱ በመገናኛ ብዙኃን ይነገራል።

ሐ/ ሥርዓተ ቀብሩ ቅዱስ ፓትሪያርኩና ብፁዓን ሊቃነ ጳጳሳት በሚገኙበት ይፈጸማል፣

መ/ በየሀገረ ስብከቱም ጸሎተ ፍትሐት ይደረግለታል።

## <u>አንቀጽ ፳፪</u>
## <u>ለቅዱስ ሲኖዶስ ተጠሪ የሆኑ መምሪያዎችና ድርጅቶች</u>

፩. ለቅዱስ ሲኖዶስ አመራር አስተዳደር ቁጥጥርና ውሳኔ አሰጣጥ የሚያግዙና አሠራሩ ቅንጅትና ጥንካሬ እንዲኖረው የሚያስችሉ ተጠሪነታቸው ለቅዱስ ሲኖዶስ የሆኑ የተለያዩ አካላት ይኖሩታል። እነዚህም፤

ሀ/ የሊቃውንት ጉባኤ
ለ/ መንፈሳዊ ፍርድ ቤት
ሐ/ የቁጥጥርና ምርመራ (ኦዲትና ኢንስፔክሽን) አገልግሎት
መ/ የሥነ-ሥርዓትና ሥነ-ምግባር ኮሚሽን
ሠ/ የልማትና ክርስቲያናዊ ተራድኦ ኮሚሽን
ረ/ የሕፃናትና የቤተሰብ ጉዳይ ድርጅት ናቸው።

የሥራ ዝርዝራቸውም በተለየ ደንብ ይወሰናል።

# ክፍል ሁለት
# ስለ ቅዱስ ሲኖዶስ ጽ/ቤት

## አንቀጽ ፳፫
## የቅዱስ ሲኖዶስ ጽሕፈት ቤትና ተግባራቱ

፩. የቤተ ክርስቲያኒቱ ቅዱስ ሲኖዶስ ለቅዱስ ሲኖዶሱ ተጠሪዎች የሆኑ መምሪያዎችንና የቅዱስ ሲኖዶሱን ሥራዎች የሚያቀናጅ የሚያደራጅና የሚያስፈጽም ተጠሪነቱ ለቅዱስ ሲኖዶስ የሆነና መቀመጫውም በጠቅላይ ቤተ ክህነት የሆነ አንድ ጽሕፈት ቤት ይኖረዋል፡፡

፪. ጽሕፈት ቤቱ በዚህ ሕግ አንቀጽ ፲፯(፲፬) መሠረት በሚመረጥና የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ በመሆን በሚሠየም ሊቀጳጳስ ወይም ኤጴስ ቆጶስ ይመራል፡፡

፫. ጽሕፈት ቤቱ በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን የተሰጠውን ኃላፊነት ለመፈጸም የሚያስችሉ ሠራተኞችና የሥራ መሣሪያዎች እንዲሁም ለሥራው የሚያስፈልገው በጀት ይኖሩታል፡፡

፬. የቅዱስ ሲኖዶስ ጽሕፈት ቤት የሚከተሉት ተግባራት ይኖሩታል፡፡

ሀ/ ቅዱስ ሲኖዶስና ቋሚ ሲኖዶስ በየስብሰባዎቻቸው የሚነጋገሩባቸውን ርእሰ ጉዳዮች (አጀንዳዎች) አዘጋጅቶ ለጉባዔዎቹ ያቀርባል፡፡

ለ/ ቅዱስ ሲኖዶስና ቋሚ ሲኖዶስ በየስብሰባዎቻቸው የተወያዩባቸውንና የወሰኑባቸውን የስብሰባ ቃለ ጉባዔዎች በተደራጀ ሁኔታ መዝግቦ ይይዛል፡፡

ሐ/ በጉባዔዎቹ የሚወሰኑ ውሳኔዎች፣ የሚወጡ ሕግጋት፣ ደንቦችና መመሪያዎች ለየሚመለከታቸው አካላት እንዲደርሱ ያደርጋል። አፈጻጸማቸውንም ይከታተላል።

መ/ ከቅዱስ ሲኖዶስ፣ ከቋሚ ሲኖዶስ፣ ከቅዱስ ፓትርያርኩ የሚወጡና ወደ ቅዱስ ሲኖዶስ ወይም ወደ ቋሚ ሲኖዶስ የሚቀርቡ ደብዳቤዎችንና ልዩ ልዩ ሠነዶችን በአግባቡ አደራጅቶና መዝግቦ ይይዛል።

ሠ/ የቅዱስ ሲኖዶሱን አጠቃላይ በጀት በማዘጋጀት ለጠቅላይ ቤተክህነት በማቅረብ ያስወስናል። የተፈቀደውን በጀትም በአግባቡና በሕጉ መሠረት በሥራ ላይ ያውላል።

ረ/ በዚህ ሕግ ድንጋጌዎች መሠረት የቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባዔ ወይም አስቸኳይ ስብሰባዎች እንዲጠሩ በሚወሰን ጊዜ የስብሰባ ጥሪዎችን በጽሑፍ ያስተላልፋል።

ሰ/ የቅዱስ ሲኖዶስና የቋሚ ሲኖዶስ ውሳኔዎች በተግባር ስለመፈጸማቸው፣ ስላለመፈጸማቸውና ያልተፈጸሙባቸውን ምክንያቶች፣ በዚህ ረገድ የተወሰደ የመፍትሔ እርምጃ ጭምር የተካተተበትን የሥራ አፈጻጸም ዘገባ ለቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባዔ በየስድስት ወሩ ያቀርባል።

ሸ/ የኤጲስ ቆጶሳትን፣ የጳጳሳትን፣ የሊቃነ ጳጳሳትንና የፓትርያርክን የሥራና የሕይወት ታሪክ መዘከሪያ መዛግብት ያደራጃል ።

ቀ/ ከቅዱስ ሲኖዶስ፣ ከቅዱስ ፓትርያርኩና ከቋሚ

ሲኖዶስ የሚሰጡትን ሌሎች ተግባራት ይፈጽማል፡፡
በ/ ጽ/ቤቱ በምልአተ ጉባኤ የጸደቀ ደንብ ይኖረዋል፡፡

## አንቀጽ ፳፬
## የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ ምርጫና የሥራ ዘመን

፩. የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ የሚመረጠው ከቅዱስ ሲኖዶስ አባላት መካከል ሲሆንምርጫው የሚካሔደውም የቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ከአባላቱ መካከል በሚሠየመውሦስት አባላት ባሉት አስመራጭ ኮሚቴ ነው፡፡

፪. አስመራጭ ኮሚቴውም ከቅዱስ ሲኖዶስ አባላት መካከል የሥራ አመራር ልምድንና ችሎታን መሠረት አድርጎ ሦስት ተወዳዳሪዎች በጉባኤ እንዲጠቆሙ ካደረገ በኋላ ምርጫው በምሥጢር የድምፅ አሰጣጡ ሥርዓት ተከናውኖ ከፍተኛ ድምፅ ያገኘው አባት በዋና ጸሐፊነት ይሠየማል፡፡ ይህም በፓትርያርኩ በተጻፈ ደብዳቤ ይገለፅለታል፡፡
፫. የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ የሲኖዶስ አባልና ጸሐፊ ሆኖ ተጠሪነቱ ለቅዱስ ሲኖዶስ ነው፡፡ ይሁንና የዕለት ከዕለት ሥራውን ከቅዱስ ፓትርያርኩ መመሪያ እየተቀበለ ይሠራል፡፡

፬. የዋና ጸሐፊው የአገልግሎት ዘመን ሦስት ዓመታት ሲሆን አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ለአንድ የምርጫ ዘመን ብቻ እንደገና መመረጥ ይችላል፡፡

፭. በዚህ አንቀጽ ንኡስ አንቀጽ ፬ የተመለከተው ቢኖርም ዋና ጸሐፊው የጸሐፊነቱን ሥራ ለመቀጠል የማያስችለው በቂ ምክንያት ካጋጠመ የምርጫ ዘመኑ ባይፈጸምም በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ውሳኔ በተጠባባቂነት በተያዘው አባት ይተካል፡፡

## አንቀጽ ፳፭
## የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ ተግባርና ኃላፊነት

የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል፡፡

፩. የቋሚ ሲኖዶስ ጸሐፊ የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ ነው፡፡

፪. ለቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ እንዲቀርቡ በቋሚ ሲኖዶስ ወይም በቅዱስ ፓትርያርኩ የሚዘጋጁ ርእሰ ጉዳዮችን (አጀንዳዎችን) ለጉባኤው ያቀርባል፡፡

፫. በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ እየተገኘ የስብሰባውን ቃለ ጉባኤ ይይዛል፤ ወይም እንዲያዝ ያደርጋል፡፡

፬. ከቅዱስ ሲኖዶሰ የሚሰጠውን ውሳኔና ትእዛዝ ለጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤትና ለሚመለከታቸው ሁሉ ያስተላልፋል፡፡

፭. የቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔዎች በተግባር ላይ መዋላቸውን ይከታተላል፡፡

፮. የቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔዎች በሥራ ላይ ካልዋሉ ሁኔታዎቹን በመከታተል ከነምክንያቶቹ ለቅዱስ ሲኖዶስ ሪፖርት ያቀርባል፡፡

፯. አስቸኳይ ጉዳይ አጋጥሞ በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን አንቀጽ ፲፱(፬) መሠረት ልዩ ስብሰባ መጥራት ሲያስፈልግ ለቅዱስ ሲኖዶስ አባላት የስብሰባ ጥሪ ያስተላልፋል፡፡

## አንቀጽ ፳፮
## የቅዱስ ሲኖዶስ ምክትል ጸሐፊ ምርጫ፣ ተግባርና ኃላፊነት

፩. የቅዱስ ሲኖዶስ ምክትል ጸሐፊ በዋና ጸሐፊው አቅራቢነት በቋሚ ሲኖዶስ ጉባኤ ይሠየማል።የሹመት ደብዳቤውም በዋና ጸሐፊው ፊርማ ይሰጠዋል።

፪. ምክትል ጸሐፊው ተፈላጊው ችሎታና ሥልጣነ ክህነት ያለው ይሆናል።

፫. ምክትል ጸሐፊው ዋና ጸሐፊው በማይኖርበት ጊዜ እርሱን ተክቶ ይሠራል።

፬. ምክትል ጸሐፊው የዋና ጸሐፊው ረዳት ሆኖ ይሠራል።

፭. የምክትል ጸሐፊው ተጠሪነት ለዋና ጸሐፊው ይሆናል።
፮. የምክትል ጸሐፊው የአገልግሎት ዘመን የዋና ጸሐፊው የአገልግሎት ዘመን ይሆናል።

## ክፍል ሦስት
## ቋሚ ሲኖዶስ

## አንቀጽ ፳፯
## የቋሚ ሲኖዶስ አባላትና ስብሰባ

፩. ቋሚ ሲኖዶስ ተጠሪነቱ ለቅዱስ ሲኖዶስ ሆኖ በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን አንቀጽ ፲፮(፲፫) መሠረት በቅዱስ ሲኖዶስ የሚቋቋምና በቅዱስ ሲኖዶሱ የጸደቁትን ሕግጋት፣ ደንቦች፣ መመሪያዎችና ውሳኔዎች በሥራ ላይ መተርጎማቸውን

የሚከታተልና የሚቆጣጠር አካል ነው፡፡

፪. ፓትርያርኩ፤ የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊውና የጠቅላይ ቤተክህነትጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ የቋሚ ሲኖዶስ ቋሚ አባላት ሲሆኑ በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ እየተመረጡ ለሦስት ወራት የሚያገለግሉ ዐራት ሊቃነ ጳጳሳት ወይም ኤጴስ ቆጶሳት በአባልነት ይኖሩታል፡፡

፫. የቋሚ ሲኖዶስ ሰብሳቢ ፓትርያርኩ ነው፡፡ ፓትርያርኩ በማይኖርበት ጊዜ ከቋሚ ሲኖዶስ አባላት መካከል እርሱ በጽሑፍ የወከለው አባት በሰብሳቢነት ያገለግላል፡፡ ሁለቱም በማይገኙበት ጊዜና የቋሚ ሲኖዶሱን ውሳኔ የሚፈልጉ አስቸኳይ ጉዳዮች ሲያጋጥሙ ከቅዱስ ፓትርያርኩ መመሪያ በመቀበልስብሰባው በቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ ይመራል፡፡

፬. ቋሚ ሲኖዶስ በሳምንት ሁለት ቀናት ይሰበሰባል፡፡ አስቸኳይ ጉዳዮች ሲኖሩ ግን ስብሰባው በማንኛውም ጊዜ ሊጠራ ይችላል፡፡

፭. የቋሚ ሲኖዶስ ስብሰባ ከአባላቱ ከግማሽ በላይ ከተገኙ የሚካሔድ ሲሆን ውሳኔ የሚተላለፈውም በአብላጫ ድምፅ ነው፡፡ ድምፅ እኩል ከተከፈለ ሰብሳቢው የደገፈው ሐሳብ ውሳኔ ሆኖ ያልፋል፡፡

## አንቀጽ ፳፰
## የቋሚ ሲኖዶስ ተግባራትና ኃላፊነቶች

ቋሚ ሲኖዶስ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል፤

፩. በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ እየተወሰኑ የሚተላለፉ መመሪያዎችና ልዩ ልዩ ጉዳዮች ተግባራዊ መሆናቸውን ይከታተላል፡፡

፪. ለቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ መቅረብ በማያስፈልጋቸውና የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት በሚሰጣቸው ውሳኔዎች ላይ የሚቀርቡ የይግባኝ (የቅሬታ)ናአቤቱታዎችን መርምሮ ይወስናል።

፫. ቅዱስ ሲኖዶስ በየጊዜው በሚያደርጋቸው ጉባኤያት የሚነጋገርባቸውን የስብሰባ አጀንዳዎች ያዘጋጃል።

፬. አስቸኳይና ድንገተኛ ጉዳይ ሲያጋጥም የቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ እንዲጠራ ይወስናል።

፭. የታላላቅ ገዳማትና አድባራት አበምኔቶችንና እመምኔቶችን ስያሜና ምደባን አስመልክቶ ከአህጉረ ስብከት ጽ/ቤቶች የሚቀርቡ የውሳኔ ሀሳቦችን ተመልክቶ በቅዱስ ፓትርያርኩ በተፈረመ ደብዳቤ ይሾማል።

፮. ለሃይማኖታዊ ሥራና ለመንፈሳዊ ትምህርት እንደዚሁም ለስብሰባና ጥናትወደ ውጭ ሀገር በሚደረጉ ምደባዎችና ጉዞዎች ላይ ውሳኔ ይሰጣል። የሚላኩ ሰዎችን ይመርጣል።

፯. የከፍተኛ መንፈሳዊ ትምህርት ተቋማትን (ኮሌጆችንና ዩኒቨርሲቲዎችን) ፕሬዚዳንትና እናዲኖች ሹመትበጠቅላይ ቤተክህነት ተጠንቶ ሲቀርብለትይሰይማል።

፰. የከፍተኛ መንፈሳዊ የትምህርት ተቋማትን (ኮሌጆችንና ዩኒቨርሲቲዎችን) እና የመንፈሳዊ ትምህርት ቤቶች ሥርዓተ ትምህርትን በጠቅላይ ቤተክህነት ተጠንቶ ሲቀርብለት መርምሮ ለቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባኤ ያቀርባል።

፱. የቅዱሳት መጻሕፍት ትርጉም በአግባቡ መከናወኑን ከሊቃውንት ጉባዔ ሲቀርብለት ትክክለኛነቱን አረጋግጦ በሥራ ላይ እንዲውል ያደርጋል።

፲. የቤተ ክርስቲያንን ትምህርት ወይም (ነገረ ሃይማኖት) አስመልክቶ በቤተ ክርስቲያን የሚከሰቱ ውስጣዊና አፍአዊ ችግሮችን በሊቃውንት ጉባዔ እያስጠና ለተገቢው ውሳኔ ለቅዱስ ሲኖዶስ ያቀርባል፡፡

፲፩. በሥራ ዘመኑ የተከናወኑ ተግባራትንና ያልተከናወኑትን በመዘርዘር ለምልዓተ ጉባኤው ዘገባ ያቀርባል፡፡

፲፪.ሌሎች በቅዱስ ሲኖዶስ የሚሰጡትን ተግባሮች ያከናውናል፡፡

## አንቀጽ ፳፱
## ስለቋሚ ሲኖዶስ ጽሕፈት ቤትና በጀት

፩. የቋሚ ሲኖዶስ ጽሕፈት ቤት የቅዱስ ሲኖዶሱ ጽሕፈት ቤት ነው፡፡የዕለት ከዕለት ሥራውም በቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ ይመራል፡፡

፪. የቋሚ ሲኖዶሱ ጽሕፈት ቤት በጀት በዓመታዊው የቅዱስ ሲኖዶስ በጀት ውስጥ የሚካተት ይሆናል፡፡

## ክፍል ዐራት
## ስለቅዱስ ፓትርያርክ
## አንቀጽ ፴
## የቅዱስ ፓትርያርክ ምርጫ

፩. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ፓትርያርክ የቤተ ክርስቲያኒቱ ሕግና ቀኖና በሚፈቅደው አኳኋን በተለይም በፍትሐ መንፈሳዊ አንቀጽ ፬ቁጥር ፷፰ እንዲሁም የቤተ ክርስቲያኒቱ ቅዱስ ሲኖዶስ በሚያወጣው

የፓትርያርክ ምርጫ ሕገ ደንብ መሠረት ተመርጦ ይሾማል፣

፪.ፓትርያርኩ ከተመረጠ በኋላ በፓትርያርክ ምርጫ ደንቡ በተደነገገው መሠረት የኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ሃይማኖትን፣ ትውፊትን እና ባህል ቀኖና ሊጠብቅ፣ አድልዎ በሌለው መልኩ ቤተክርስቲያኒቱን ሊያስተዳድር የቃለ መሐላው ይዘትም በፓትርያሪክ ምርጫ ሕገ ደንብ በተመለከተው መሠረት ይሆናል።

፫. ፓትርያርኩ እንደተመረጠ ቃለ መሐላ ይፈጽማል ብዙም ሳይዘገይ የቤተ ክርስቲያን ሥርዓት በሚፈቅደው መሠረት ሥርዓተ ሢመተ ፓትርያርክ ይፈጸምለታል።

## አንቀጽ ፴፩
## የቅዱስ ፓትርያርክ የመዓርግ ስምና መንበር

፩. ፓትርያርኩ ከተሾመበት ቀን ጀምሮ "ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ዕገሌ ፓትርያርክ ርእሰ ሊቃነ ጳጳሳት ዘኢትዮጵያሊቀ ጳጳስ ዘአክሱም ወዕጨጌ ዘመንበረ ተክለ ሃይማኖት" እየተባለ ይጠራል። ስሙም በመላዋ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን በጸሎት ይጠራል።

፪. ፓትርያርኩ በሀገር ውስጥም ሆነ በውጭ ሀገር ለሚኖሩ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ካህናትና ምእመናን መንፈሳዊ መሪና አባት ነው። በሀገር ውስጥና በውጪ ሀገርም ቤተ ክርስቲያኗን ይወክላል።

፫. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ፓትርያርክ መንበር በአዲስ አበባ ከተማ በመንበረ ፓትርያርክ ቅድስተ ቅዱሳን ማርያም ገዳም ነው።

፬. ከዚህ በፊት የነበረ ፓትርያርክ በሚጠራበት ስመ

ፕትርክና የተሠየመ እንደሆነ ቅዱስ ፓትርያርኩ በዚህ ስም የሚጠራው ስንተኛው ፓትርያርክ መሆኑን የሚያመለክት ቀዳማይ ወይም ካልአይ የሚል ቅፅል እየተጨመረ የሚጠራ ይሆናል፡፡

## አንቀጽ ፴፪
## የቅዱስ ፓትርያርኩ ተግባራትና ኃላፊነቶች

ቅዱስ ፓትርያርኩ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል፡፡

፩. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያንን ሃይማኖት፣ ትውፊትና ቀኖና ይጠብቃል፣ ያስጠብቃል፡፡

፪. የቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባኤንና ቋሚ ሲኖዶስን በሊቀመንበርነት ይመራል፡፡

፫. በፍትሕ መንፈሳዊ አንቀጽ ፭ እና በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን አንቀጽ ፴፭ መሠረት ቅዱስ ሲኖዶስ ለመረጣቸው መነኮሳትና ቆሞሳት ከሊቃነ ጳጳሳት ጋር በመሆን በአንብሮተ እድ የኤጲስ ቆጶስነት ሹመት ይሰጣል፡፡

፬.ቅዱስ ሲኖዶስ በሚያወጣው መመሪያ መሠረት ለኤጴስ ቆጶሳት የሊቀ ጵጵስና መዓርግ ይሰጣል፡፡

፭. በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን አንቀጽ ፲፯(፲፬) መሠረት ለሚሠየሙ የሥራ ኃላፊዎች የሹመት ደብዳቤ ይሰጣል፡፡

፮. በየአህጉረ ስብከቱ ሊቃነጳጳሳት እየተመረጡ ለሚቀርቡለት በቀደምትነትና በታሪክ ለታወቁ የታላላቅ ገዳማት አበምኔቶችና የከፍተኛ አድባራት አስተዳዳሪዎች የመዓርግ ስምና ሹመት ይሰጣል፡፡

፯. የቤተ ክርስቲያንን ጉዳይ አስመልክቶ ከመንግሥት ጋር የሚደረጉ ግንኙነቶችን፣ እንደዚሁም ሌሎች ቤተ ክርስቲያንን የሚመለከቱ ዐበይት ጉዳዮችን ሁሉ በቅዱስ ሲኖዶስ እያስወሰነ አስፈላጊውን ተግባር ያከናውናል።

፰. በቅዱስ ሲኖዶስ የወጡ ሕጎችን፤ የተላለፉ መመሪያዎችንና የተሰጡ ውሳኔዎችን ለሚመለከታቸው ሁሉ በፊርማው ያስተላልፋል፣ በተግባር ላይ መዋላቸውንም ይከታተላል፣ ይቆጣጠራል።

፱. በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን ለተሾሙ የባንክ ገንዘብ ለማንቀሳቀስ ሥልጣን የተሰጣቸው የሥራ ኃላፊዎች ለሚመለከታቸው ባንኮች ደብዳቤ ይጽፋል ።

፲. በውጭ ሀገር በሚገኙ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን አህጉረ ስብከት ለማገልገል ወይም የነፃ ትምህርት ለመማር የሚላኩ ካህናትና የቤተ ክርስቲያን አገልጋዮች በዚህ ሕግ አንቀጽ ፲፰(፲፯) መሠረት በቋሚ ሲኖዶስ ተመርጠው ሲቀርቡለት እንዲላኩ ያደርጋል።

፲፩. ከውጭ ሀገር የሚመጡ እንግዶችን በው ጭ ጉዳይ መምሪያ ኃላፊ አቅራቢነት እየተቀበለ ያነጋግራል።

፲፪. በውጭ ሀገርም ሆነ በሀገር ውስጥ በሚደረጉ ስብሰባዎችና ልዩ ልዩ ጉዳዮች ላይ ቤተ ክርስቲያንን በመወከል ይገኛል ወይም ሌላ ሰው ይወክላል። ስለተከናወነው ተግባርም ለቅዱስ ሲኖዶስ ሪፖርት እንዲቀርብ ያደርጋል

፲፫. በቤተ ክርስቲያኒቱ ታላላቅ ዓመታውያን በዐላት ላይ አስፈላጊ በሆነ ጊዜ ሁሉ እየተገኘ ለምእመናን ቃለ ምዕዳን እና ቡራኬ ይሰጣል።

፲፬. ቅዱስ ፓትርያርኩ የቤተ ክርስቲያኒቱ ርእስ እንደመሆኑ መጠን ይህን ሕገ ቤተክርስቲያንን ጠብቆ ለቤተ ክርስቲያኒቱ አጠቃላይ አመራር ይሰጣል።

## አንቀጽ ፴፫
## ስለ ቅዱስ ፓትርያርኩ ከመዓርግ መውረድ

፩. ቅዱስ ፓትርያርኩ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ፓትርያርክ ሆኖ ከተሾመ በኋላ የተቀበለውን ኃላፊነት በመዘንጋት

ሀ/ የኦርቶዶክስ ተዋሕዶሃይማኖትን የሚያፋልስ፣ ቀኖና ቤተ ክርስቲያንን የማይጠብቅና ቤተ ክርስቲያንን የሚያስነቅፍ ተግባርን ፈጽሞ ከተገኘና ይኸውም በቅዱስ ሲኖዶሱ ከተረጋገጠ፤

ለ/ በፍትሕ መንፈሳዊ አንቀጽ ፰ ከቁጥር ፻፹፪ እስከ ፪፻፳ በተደነገገው መሠረት በደለኛ መሆኑ በቅዱስ ሲኖዶሱ ከታመነበት፤

ሐ/ በቃሉ የማይገኝና በዚህ ሕግ አንቀጽ ፴(፪) መሠረት በተሾመበት ቀን የፈጸመውን ቃለ መሐላ ያልጠበቀ፣ በአጠቃላይ ታማኝነቱና መንፈሳዊ አባትነቱ በካህናትና በምእመናን ዘንድ ተቀባይነት ያጣ ሆኖ ቤተ ክርስቲያኒቱን የሚያስነቅፍ መሆኑ በተጨባጭ ከተረጋገጠ በቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔ ከሥልጣኑ ይወርዳል፤ በምትኩም ሌላ ፓትርያርክ ተመርጦ ይሾማል።

፪. ከዚህ በላይ በተደነገገው መሠረት ከሥልጣኑ የተገለለ ፓትርያርክ በቀኖና ተወስኖ በገዳም ይቀመጣል።

፫.ከሥልጣኑ የተገለለው ፓትርያርክ በገዳም አልቀመጥም በቀኖናም አልወሰንም በማለት እምቢተኛ ከሆነ ተወግዞ

ከቤተ ክርስቲያን አንድነት ይለያል
፬. ፓትርያርኩ መንፈሳዊ ሥራውን በማካሔድ ላይ እያለ እሥራትና ግዞት ቢደርስበት ቤተክርስቲኒቱ በቅዱስ ሲኖዶስ ትመራለች እንጂ ሌላ ፓትርያርክ አይሾምም፡፡

፭. ከዚህ በላይ የተዘረዘረው ሁሉ ፍትሕ መንፈሳዊ በሚያዝዘው መሠረት ይፈጸማል፡፡

## አንቀጽ ፴፩
## ስለ አቃቤ መንበረ ፓትርያርክ

፩. ቅዱስ ፓትርያርኩ በሞት ሲለይ ወይም ከኃላፊነት ሲገለል የቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊወይም ቋሚ ሲኖዶሱ በሚጠራው አስቸኳይ ስብሰባ ቅዱስ ሲኖዶስ በሹመት ቀደምትነት ካላቸውና ሙሉ ጤነኛ ከሆኑት ሦስት ሊቃነ ጳጳሳት መካከል መርጦ በዕለቱ ዐቃቤ መንበረ ፓትርያርክ ይሾማል፡፡

፪. የተተኪው ፓትርያርክ ምርጫ እስከሚጠናቀቅ ድረስ አቃቤ መንበረ ፓትርያርኩ የቅዱስ ሲኖዶስ ሰብሳቢ ሆኖ የቤተ ክርስቲያንን አገልግሎት ይፈጽማል፡፡

፫. አቃቤ መንበረ ፓትርያርኩ በኃላፊነቱ የሚቆየው የተተኪው ፓትርያርክ ምርጫ እስከሚፈጸም ይሆናል፡፡ የተተኪው ፓትርያርክ ምርጫና ሹመትም እንደጊዜውና እንደሥራው ሁኔታ እየታየ ከዐርባ (፵) እስከ ሰማንያ (፹) ቀናት ባለው ጊዜ ይፈጸማል፡፡
፬. ዐቃቤ መንበረ ፓትርያርኩ አስፈላጊ የቤተ ክርስቲያን ሥራዎችን ከቋሚ ሲኖዶስ ጋር እየመከረ ያከናውናል፡፡

፭.በፓትርያርኩ ምርጫ ጊዜም የቅዱስ ሲኖዶስ ሊቀመንበር ሆኖ ምርጫውን ያስፈጽማል፤ እርሱ ግን ከምርጫው አይገባም፡፡

## አንቀጽ ፴፭
## ስለ ኤጴስ ቆጶሳት ምርጫ

፩. በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ቀኖና መሠረት የኤጴስ ቆጶሳት ምርጫ የሚፈጸመው፡-

ሀ/ ኤጲስ ቆጶስ እንዲሾም አስፈላጊ መሆኑ በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ሲታመንበትና ሲወሰን፣

ለ/ በሥርዓተ ምንኩስና በድንግልና መንኩሰው በክህነት ቤተ ክርስቲያንን ከሚያገለግሉና ለኤጲስ ቆጶስነት ብቁ ከሆኑ መነኮሳትና ቆሞሳት መካከል በቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባኤ በሚቋቋም አስመራጭ ኮሚቴ አማካይነት ተገምግመውና ተመዝነው በቅዱስ ሲኖዶስ ተቀባይነት ሲያገኙ ለውድድር ይቀርባሉ ።

፪. ለኤጲስ ቆጶስነት ዕጩ ለመሆን የሚያበቁ መስፈርቶችና የምርጫ ሥርዓት በቅዱስ ሲኖዶሱ በሚወጣ ዝርዝር ደንብ መሠረት ይወሰናል፡፡

## አንቀጽ ፴፮
## የኤጴስ ቆጶስ ሹመትና የመዓርግ ስም

፩. ኤጲስ ቆጶሱ ከተሾመበት ቀን ጀምሮ ብፁዕ አቡ ዕገሌ ተብሎ በቅዱስ ሲኖዶስ በሚሰጠው የኤጲስ ቆጶስነት ስም ይጠራል። ስሙም በሀገረ ስብከቱ ባሉት ገዳማት፣ አድባራትና የአጥቢያ አብያተ ክርስቲያናት ዘወትር በጸሎት ይጠራል።

፪. ቤተ ክርስቲያን ባለችበት ቦታ ሁሉ አንድ ሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስ ወይም ኤጴስ ቆጶስ በአገልግሎት ጊዜ ከደረሰ በተገኘበት ጸሎት ላይ ስሙ ይጠራል፡፡

፫. ኤጲስ ቆጶሱ በቤተ ክርስቲያኒቱ ቀኖና መሠረት በአንብሮተ እድ የሚሾመው ቅዱስ ሲኖዶስ በወሰነው ሀገረ ስብከት ወይም አስፈላጊ በሆነ የሥራ ቦታ ነው፡፡

## <u>አንቀጽ ፴፯</u>
## <u>የሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስና ኤጴስ ቆጶስ ተግባርና ኃላፊነት</u>

ሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስ ወይም ኤጲስ ቆጶስ ተጠሪነቱ ለቅዱስ ሲኖዶስ ሆኖ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል፡፡

፩. በተሾመበት ሀገረ ስብከት ካህናትንና ምእመናንን የመምራት፣ የማስተማር፣ ምሥጢራተ ቤተ ክርስቲያንን የመፈጸምና የማስፈጸም ሙሉ ሥልጣን አለው፡፡

፪. በሀገረ ስብከቱ ውስጥ በሚገኙት ገዳማት፣ አድባራትና የገጠር አብያተ ክርስቲያናት ውስጥ ላሉት ካህናትና ምእመናን መንፈሳዊ አባት እና መሪ ነው፡፡

፫. በፍትሐ መንፈሳዊ አንቀጽ ፳ እና ፺ በተደነገገው መሠረት ሥራውን ያከናውናል፡፡ ዝርዝር ኃላፊነቱና ተግባሩ በቃለ ዓዋዲ ይወጣል፡፡

## <u>አንቀጽ ፴፰</u>
## <u>የሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስና የኤጴስ ቆጶስ ግዴታዎች</u>

፩. ሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስ ወይም ኤጲስ ቆጶሱ በተሾመበት ሀገረ ስብከት ይኖራል፡፡

፫. ኤጲስ ቆጶሱ በቤተ ክርስቲያኒቱ ቀኖና መሠረት በአንብሮተ እድ የሚሾመው ቅዱስ ሲኖዶስ በወሰነው ሀገረ ስብከት ወይም አስፈላጊ በሆነ የሥራ ቦታ ነው።

## አንቀጽ ፴፯
## የሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስና ኤጴስ ቆጶስ ተግባርና ኃላፊነት

ሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስ ወይም ኤጲስ ቆጶስ ተጠሪነቱ ለቅዱስ ሲኖዶስ ሆኖ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል።

፩. በተሾመበት ሀገረ ስብከት ካህናትንና ምእመናንን የመምራት፣ የማስተማር፣ ምሥጢራተ ቤተ ክርስቲያንን የመፈጸምና የማስፈጸም ሙሉ ሥልጣን አለው።

፪. በሀገረ ስብከቱ ውስጥ በሚገኙት ገዳማት፣ አድባራትና የገጠር አብያተ ክርስቲያናት ውስጥ ላሉት ካህናትና ምእመናን መንፈሳዊ አባት እና መሪ ነው።

፫. በፍትሐ መንፈሳዊ አንቀጽ ፭ እና ፮ በተደነገገው መሠረት ሥራውን ያከናውናል። ዝርዝር ኃላፊነቱና ተግባሩ በቃለ ዓዋዲ ይወጣል።

## አንቀጽ ፴፰
## የሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስና የኤጴስ ቆጶስ ግዴታዎች

፩. ሊቀ ጳጳስ፣ ጳጳስ ወይም ኤጲስ ቆጶሱ በተሾመበት ሀገረ ስብከት ይኖራል።

፪. በቅዱስ ፓትርያርኩ ፈቃድ ወይም በሥራ ወይም በሕመም ምክንያት ካልሆነ በቀር ከሀገረ ስብከቱ ውጭከ0ሥራ አምስት ቀናት የበለጠ መቆየት የለበትም፡፡

፫. በፍትሐ መንፈሳዊ አንቀጽ ፭ ቁጥር ፪፻፮-፪፻፩ በተደነገገው መሠረት ሳይፈቀድለት ወይም ሳይጠይቅ ወይም ሳይጠየቅ በሌላው ሀገረ ስብከት ገብቶ ክህነት መስጠት፣ መዳኘት፣ አዲስ የቤተ ክርስቲያን መሠረት ማስቀመጥና የመሳሰሉትን 0በይት ተግባራት መፈጸም አይችልም፡፡ ይህን አድርጎ ቢገኝ የተጠቀሰው የፍትሐ መንፈሳዊ ድንጋጌ በሚያዝዘው መሠረት ይፈጸማል፡፡

፬. ከዚህ በላይ በዚህ አንቀጽ ቁጥር ፫ የተደነገገው እንደተጠበቀ ሆኖ የሀገረ ስብከቱ ሊቀጳጳስ፣ጳጳስ ወይምኤጴስ ቆጶሱ በሕመም ወይም በሞት ምክንያት በሥራ ላይ በማይኖርበት ጊዜ ወደሌላው ሀገረ ስብከት ሔደው መአርገ ዲቁናና ቅስና ለመቀበል የሚጠይቁ ካሉ የትምህርት ችሎታቸውንና ከሀገረ ስብከታቸው የተሰጣቸውን ማስረጃ እያረጋገጠ መዓርጉን ሊሰጣቸው ይችላል፡፡

፭. ያለቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔ የሊቀጳጳስነት፣ የጳጳስነትን ወይም የኤጴስ ቆጶስነትን መዓርግ በፈቃድ ለመተው አይፈቀድም፡፡

፮. ሊቀጳጳሱ፣ጳጳሱ ወይም ኤጴስ ቆጶሱ ከዓለም በሞት ሲለይ አስከሬኑ የኤጴስ ቆጶስነት ተልእኮውን ሲፈጽም ከኖረበት ሀገረ ስብከት ያርፋል፡፡

## አንቀጽ ፴፱
## ስለ ሊቃነ ጳጳሳት፣ ጳጳሳትና ኤጴስ ቆጾሳት ዝውውር

፩. በፍትሕ መንፈሳዊ አንቀጽ ፭ ቁጥር ፻፶፰ በተደነገገው መሠረት አንድ ኤጴስ ቆጾስ ጳጳስና ሊቀ ጳጳስ ከተሾመበት ሀገረ ስብከት ሊዛወር አይችልም።

፪. ከዚህ በላይ የተደነገገው እንደተጠበቀ ሆኖ በቅዱስ ሲኖዶስ ሲታመንበት፤

ሀ/ በሥራ ወይም በሌላ አጥጋቢ ምክንያት ወደ ሌላ ቦታ እንዲዛወር አስፈላጊ ከሆነ፤

ለ/ ኤጲስ ቆጾሱ፣ጳጳሱ ወይም ሊቀ ጳጳሱ በተመደበበት ቦታ ለመቆየት አስቸጋሪ ሆኖ ከተገኘ በቅዱስ ሲኖዶስ ተጠንቶ በውሳኔ ሊዛወር ይችላል።

፫. በተመደበበት ሀገረ ስብከት ወይም የሥራ ቦታ መቆየት አይችልም ተብሎ በቅዱስ ሲኖዶስ የተወሰነበት ወይም የተወሰነለት ኤጴስ ቆጾስ፣ ጳጳስና ሊቀ ጳጳስ በሌላ ቦታ ሊመደብ የሚችለው በቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔ ነው።

፬. ኤጴስ ቆጾሱ፣ ጳጳሱና ሊቀ ጳጳሱ ከዚህ በላይ በንዑስ አንቀጽ ፪ ከተዘረዘሩት ምክንያቶች ውጪ በሌላ ምክንያት ሊዛወር አይችልም

## አንቀጽ ፵
## የኤጴስ ቆጾስ፣ ጳጳስና ሊቀ ጳጳስ ከመዓርግ መውረድ

በዚህ ሕግ አንቀጽ፴፫ ሥር ስለ ቅዱስ ፓትርያርኩ ከመዐርግ መውረድን አስመልክቶ የተደደነገገው ለኤጲስ ቆጾሱም፣ ለጳጳሱም፣ ለሊቀ ጳጳሱምተፈጻሚ ይሆናል።

# ክፍል ስድስት
# ስለ ጠቅላይ ቤተ ክህነት
## አንቀጽ ፴፩
## የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት

፩. የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት የቤተ ክርስቲያንን የሥራ አስፈጻሚነትና የአስተዳደር ተግባር የማከናወን ሥልጣን የተሰጠው ከፍተኛ የቤተ ክርስቲያኒቱ አካል ነው።

፪. ጠቅላይ ቤተ ክህነት ከቅዱስ ሲኖዶስ አባላት መካከል በሲኖዶሱ አባላት የሚመረጥና በቅዱስ ፓትርያርኩ ፊርማ በተጻፈ ደብዳቤ የሚሾም አንድ ጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ ይኖረዋል።

፫. የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት በጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ ጠቋሚነት ከሚቀርቡ ሦስት ዕጩዎች መካከል በቋሚ ሲኖዶስ የሚመረጥ ምክትል ሥራ አስኪያጅ ይኖረዋል።

፬. የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤትበሥሩ ሆነው የቤተ ክርስቲያኒቱን የአስፈጻሚነትና የአስተዳደር ተግባራት የሚያከናውኑ የተለያዩ መምሪያዎች ይኖሩታል።

### ሀ. መምሪያዎችና የአገልግሎት የሥራ ዘርፎች፡-

1. ስብከተ ወንጌልና ሐዋርያዊ ተልዕኮ መምሪያ
2. ትምህርትና ማሠልጠኛ መምሪያ
3. ካህናት አስተዳደር መምሪያ
4. ሰበካ ጉባኤ ማደራጃ መምሪያ
5. የገዳማት መምሪያ
6. ሰንበት ት/ቤቶች ማደራጃ መምሪያ
7. ሕግ አገልግሎት መምሪያ
8. የሕግ አማካሪ

9. አስተዳደር መምሪያ
10. በጀትና ሂሣብ መምሪያ
11. ውጭ ጉዳይ መምሪያ
12. ቅርሳቅርስ መምሪያ
13. እቅድና ልማት መምሪያ
14. ቤቶችና ሕንጻዎች አስተዳደርና ልማት ድርጅት
15. የመሪ ዕቅድ መምሪያ
16. የህዝብ ግንኙነት መምሪያ

**ለ. ድርጅቶች፡-**

1. ትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት
2. ትንሣኤ ማሳተሚያ ድርጅት
3. አልባሳት ማደራጃና ምርት ሥርጭት
4. ቁልቢ ቅ/ገብርኤል ንዋየ ቅድሳት ማደራጃ
5. የጐፋ ጥበበ እድ ማሠልጠኛ

፯. በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ ፫ የተጠቀሰው ምክትል ሥራ አስኪያጅ እንዲሁም በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ ፬ መሠረት የሚቋቋሙት መምሪያ ኃላፊዎች ተጠሪነታቸው ለጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ ይሆናል፡፡ ሆኖም በዚህ ሕግ አንቀጽ ፳፪ (፩) የተጠቀሰው እንደተጠበቀ ሆኖ ቅዱስ ሲኖዶሱ አስፈላጊ ሆኖ ያገኘውን መምሪያ በቀጥታ ለራሱ ተጠሪ ከማድረግ ይህ ድንጋጌ አያግደውም፡፡

፰. የተወሰኑ መምሪያዎች ቅዱስ ሲኖዶሱ በሚወስነው መሠረት በሊቃነ ጳጳሳት የበላይ ኃላፊነት ሊመሩ ይችላሉ፡፡ ዝርዝር የሥራ መመሪያም ይወጣላቸዋል፡፡

፱. የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት የመምሪያ ኃላፊዎች በአባልነት የሚገኙበትና በጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ ሰብሳቢነት የሚመራ አንድ የአስተዳደር ጉባዔ ይኖረዋል፡፡

፰. ተግባርና ኃላፊነቱ በቃለ አዋዲው የሚገለፅ በጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ ሰብሳቢነት የሚመራ አንድ የመንበረ ፓትሪያርክ አጠቃላይ ሰበካ መንፈሳዊ አስተዳደር ጉባኤ ሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ ይኖረዋል፡፡
፱. የጠቅላይ ቤተ ክህነቱ ጽሕፈት ቤት ተጠሪነቱ ለቅዱስ ሲኖዶስ ይሆናል።

## አንቀጽ ፴፪
## የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ተግባራትና ኃላፊነት

የጠቅላይ ቤተ ክሕነት ጽሕፈት ቤት የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል፡-

፩. ቅዱስ ሲኖዶስ ለቤተ ክርስቲያን አስተዳደር በየጊዜው የሚወስናቸውን ጉዳዮችና ከቤተ ክርስቲያኒቱ መምሪያዎች፣ ከልዩ ልዩ መሥሪያ ቤቶችም ሆነ ከየሀገረ ስብከቱ የሚቀርቡትን ጥያቄዎች ሁሉ በቤተ ክርስትያኒቱ ሕግጋት መሠረት ይፈጽማል፣ ያስፈጽማል፡፡

፪. በዚህ ሕግ ወይም በሌላ ሕግ ተለይተው ለሌላ የቤተ ክርስቲያኒቱ የአስተዳደር አካላት ያልተሰጡ መምሪያዎችንና በቤተ ክርስቲያኒቱ ሥር የሚገኙ የሥራ ዘርፎችን ሁሉ ያስተዳራል፣ ይመራል፡፡
፫. ከቤተ ክርስቲያኒቱ አቋም ጋር የሚስማሙ ሥራዎች በማካሔድና የገንዘብ ምንጭ በማስገኘት የቤተ ክርስቲያን ሀብትና ንብረት የሚለማበትንና የሚጠበቅበትን ዘዴ እያጠና ለቅዱስ ሲኖዶስ ያቀርባል፣ ሲፈቀድለትም በቤተ ክርስቲያኒቱ የፋይናንስና የንብረት አስተዳደር ደንብ መሠረት ተግባራዊ ያደርጋል፡፡

፬. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያኒቱ ገንዘብ በቤተ ክርስቲያኒቱ የፋይናንስና የንብረት አስተዳደር ደንብ መሠረት ገቢ

መሆኑን በሕጋዊ መንገድ ወጭ እየሆነ ለቤተ ክርስቲያኒቱ አገልግሎት መዋሉን ያረጋግጣል፡፡

፭. የየዓመቱን የጠቅላይ ቤተ ክህነቱን የሥራ ዕቅድ በግንቦት ወር (በርክበ ካህናት) ለሚካሔደው የቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባዔ ያቀርባል፣ ሲፈቅድም ተግባራዊ ያደርጋል፡፡

፮. የየመምሪያዎቹ፣ የድርጅቶችና የልዩ ልዩ የሥራ ዘርፎች የሥራ ኃላፊዎችን የሥራ ዝውውር ዕድገት በተመለከተ በጠቅላይ ቤተክህነት ሥራ አስኪያጅ አቅራቢነት ተጠንቶና ቅዱስ ፓትርያርኩ ሲስማማበት በሥራ ላይ እንዲውል ያደርጋል፡፡

፯. ጠቅላይ ጽሕፈት ቤቱ፣ በየድርጅቱና በየሥራ ዘርፉ ያለውን የሠራተኛ ቅጥር፣ ዝውውርና ዕድገት፣ስንበት፣ የሚመለከቱ ጉዳዮች በቤተ ክርስቲያኒቱ የሠራተኞች አስተዳደር ደንብ መሠረት መፈጸሙን ያረጋግጣል፣ ያስፈጽማል፡፡

፰. በቤተ ክርስቲያኒቱ ስም የተቋቋሙትን እና የሚቋቋሙትን የልማት፣ የበጎ አድራጎት፣ የትምህርት ተቋማትእና የማምረቻ ድርጅቶችን ሁሉ ይመራል፣ ይቆጣጠራል፡፡

፱. ማንኛውም የቤተ ክርስቲያኒቱ ንብረት፣ የገንዘብ ገቢና ወጭ በቤተ ክርስቲያኒቱ የፋይናንስና የንብረት አስተዳደር ደንብ መሠረትና በሕግ ፊት ተቀባይነት ባለው የሒሳብ አያያዝ ሥርዓት መሠረት መከናወኑን ይከታተላል፣ይቆጣጠራል፡፡

፲. በየዓመቱና አስፈላጊ ሆኖ በሚገኝበት ጊዜ ሁሉ የራሱን፣ በሥሩ የሚገኙትን መምሪያዎች፣ ድርጅቶችና አህጉረ ስብከት በአጠቃላይ የቤተ ክርስቲያኒቱ የገንዘብና የንብረት

አያያዝና አመዘጋገብ ቋሚ ሲኖዶሱ በሚሠይመው የውጭ ኦዲተር እንዲመረመሩ ያደርጋል። ውጤቱም ለቅዱስ ሲኖዶስ እንዲቀርብ ያደርጋል።
፲፩. በውጭ ሀገር የሚገኙትን አህጉረ ስብከትና አብያተ ክርስቲያናት የሥራ ሒደት ይከታተላል፣ይቆጣጠራል።

## አንቀጽ ፵፫
## የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ አመራረጥና ሹመት

፩. ጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ በቅዱስ ሲኖዶስ በሚሠየም አስመራጭ ኮሚቴ አማካኝነት ለውድድር ከቀረቡ ሦስት ዕጩ የቅዱስ ሲኖዶስ አባላት መካከል በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ተመርጦ በፓትርያርኩ ፊርማ ይሾማል።
፪. የጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ የአገልግሎት ዘመን ሦስት ዓመታት ነው። አስፈላጊ ሆኖ ከተገኘም ለአንድ ተጨማሪ የሥራ ዘመን እንደገና እንዲያገለግል ሊመረጥ ይችላል።

፫. ጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ ሥራውን እንዲቀጥል የማያስችል ምክንያት ካጋጠመ የአገልግሎት ዘመኑ ሳይፈጸም በቅዱስ ሲኖዶስ ጉባኤ ውሳኔ በተጠባባቂው ሊተካ ይችላል።

## አንቀጽ ፵፬
## የጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ ተግባራትና ኃላፊነቶች

የጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ ተጠሪነት ለቅዱስ ሲኖዶስና ለቅዱስ ፓትርያርኩ ሆኖ ከዚህ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል።

፩. የቤተ ክርስቲያኒቱ ዓመታዊ የሥራ ዕቅድና በጀት በየደረጃው ከሚገኙ የቤተ ክርስቲያኒቱ አካላትና የሥራ

ዘርፎች ተሰብስቦ እንዲዘጋጅ ያደርጋል፡፡

፪. በየሦስት ወሩ አንድ ጊዜ የሥራ አፈጻጸም ዘገባ ለቋሚ ሲኖዶሱ ያቀርባል፡፡
፫. በየዓመቱ ሁለት ጊዜያት (በጥቅምትና በርክበ ካህናት) በሚካሔደው የቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባኤ የሥራ አፈጻጸም ዘገባ ያቀርባል፡፡

፬. ሥልጣነ ክህነት ያላቸው ሆነው በነገረ እግዚአብሔር ወይም በአንድ የጉባኤ ትምህርት የተመረቁ፣ በቂ የቤተ ክርስቲያን ትምህርት ያላቸውና በአስተዳደር ችሎታቸው ብቁ የሆኑ ሰዎችን ለምክትል ሥራ አስኪያጅነት ዕጩ በማድረግ በቋሚ ሲኖዶስ ያስመርጣል፡፡
፭. በቋሚ ሲኖዶስ የሚመረጠው ምክትል ዋና ሥራ አስኪያጅ በቅዱስ ፓትርያርኩ በሚፈረም ደብዳቤ ይሾማል፡፡

፮. ከመደበኛው በጀት ሌላ ድንገተኛ ወጭ በሚያስፈልግበት ጊዜ በቋሚ ሲኖዶስ እያስወሰነ ከመጠባበቂያው በጀት ላይ ወጭ በማድረግ በሥራ ላይ ያውላል፡፡

፯. ቤተ ክርስቲያኒቱን ወክሎ በቤተ ክርስቲያኒቱ ስም ይከሳል፣ ይከሰሳል፡፡ ለዚህም አስፈላጊውን የውክልና ሥልጣን ይሰጣል፡ ፡ ሆኖም የቤተ ክርስቲያኒቱን ሀብትና ንብረት የሚመለከቱ ውሎች ሲሆኑ በቋሚ ሲኖዶሱ እያስወሰነ ይዋዋላል፡፡

፰. በበጀት የተመደበውን የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ገንዘብና ንብረት በፈርማው ያንቀሳቅሳል፡፡

፱. በጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ሥር በሚገኝ መምሪያ፣ ወይም ድርጅት፣ ወይም የትምህርት ተቋም፣ ወይም በሌላ የሥራ ዘርፍ ስም የተከፈቱትንና የሚከፈቱትን

የባንክ ሒሳቦች ከቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ ወይም ሒሣቡ በስሙ ከተከፈተለት መሥሪያ ቤት ኃላፊ ጋር በጣምራ ፊርማ ያንቀሳቅሳል።

፲. የጠቅላይ ቤተ ክህነቱን የባንክ ሂሳብ ከቅዱስ ሲኖዶስ ዋና ጸሐፊ ጋር በመሆን በጣምራ ፊርማ ያንቀሳቅሳል።

፲፩. ቅዱስ ሲኖዶሱ በልዩ ሁኔታ ካልወሰነ በቀር ጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ የማይፈርምበት ወይም የማያውቀው የባንክ ሒሳብ ሕጋዊነት አይኖረውም።

፲፪. በጥቅምት ወር በሚደረገው የሰበካ አስተዳደር አጠቃላይ መንፈሳዊ ጉባኤላይ የጠቅላይ ቤተ ክህነቱን ጽሕፈት ቤት የሥራ አፈጻጸም የክንውን ሪፖርት ያቀርባል።

## አንቀጽ ፵፩
## ስለምክትል ሥራ አስኪያጅ

የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ምክትል ሥራ አስኪያጅ በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን አንቀጽ ፵፩(፫) መሠረት የሚመረጥና ተጠሪነቱ ለጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ ሲሆን ከዚህ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል።

፩. ዋናው ሥራ አስኪያጅ በማይኖርበት ጊዜ ዋናውን ሥራ አስኪያጅ ወክሎ ይሠራል።

፪. ከጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ የሚሰጠውን ሥራ ይፈጽማል፣

፫. የምክትል ሥራ አስኪያጁ የሥራ ዘመን የዋና ሥራ አስኪያጁ የሥራ ዘመን ይሆናል።

፬. ምክትል ሥራ አስኪያጅ የሥራ ዘመኑ ሳይፈጸም ሥራውን መቀጠል የማያስችለው ጉዳይ ሲያጋጥም በአንቀጽ ፵፫(፫) ላይ ስለ ዋናው ሥራ አስኪያጅ የተደነገገው ይፈጸማል፡፡

## አንቀጽ ፵፮
## ስለጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽ/ቤት የአስተዳደር ጉባኤ

፩.የጠቅላይ ቤተ ክህነት የአስተዳደር ጉባኤ፤ የመምሪያና የድርጅት ኃላፊዎች በአባልነት የሚገኙበት ማንኛውንም የቤተ ክርስቲያኒቱን መንፈሳዊ፣ ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ የአስተዳደር ጉዳዮች እና ጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ በአስተዳደር ጉባኤ እንዲታዩና እንዲወሰኑ ያቀረባቸውን ጉዳዮች በቤተ ክርስቲያኒቱ ሕግጋት፣ ደንቦችና ልዩ ልዩ መመሪያዎች መሠረት ማየትና መወሰን የሚችል ጉባኤ ነው፡፡
፪. የአስተዳደር ጉባኤው ስብሳቢ የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ ነው፡፡ ጠቅላይ ሥራ አስኪያጁ በሌለበት ጊዜ ምክትል ሥራ አስኪያጅ ጉባኤውን በሰብሳቢነት ይመራል፡፡

፫. የአስተዳደር ጉባኤው የሚከተሉት ዋና ዋና ተግባራት ይኖሩታል፡-

ሀ/ ከእያንዳንዱ የጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት፣ መምሪያዎች ድርጅቶችና የሥራ ዘርፍ በሚቀርቡ አስተዳደራዊ ጉዳዮች ላይ እየተወያየና የሥራ አፈጻጸም ስልት እያወጣ ይወሰናል፡፡

ለ/ የአስተዳደር ችግሮች ሲፈጠሩ (ሲከሰቱ) እያጠናና በጥናቱ ውጤት ላይ እየተወያየ ይወሰናል፡፡

ሐ/ ከየሀገረ ስብከቱ በይግባኝ የሚቀርቡለትን አስተዳደራዊ ጉዳዮች ተመልክቶ ይወስናል፡፡

## ክፍል ሰባት
## ስለ አህጉረ ስብከት

### አንቀጽ ፵፮
### የአህጉረ ስብከት መቋቋም

፩. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን አህጉረ ስብከት በሁለት ክፍላት ይመደባሉ፡፡ እነርሱም፡-
ሀ/ በሀገር ውስጥ ከአዲስ አበባ ጀምሮ በመላ ኢትዮጵያያሉትን፣

ለ/ በውጭ ሀገር ከቅድስት ሀገር እየሩሳሌም ጀምሮ በየክፍላተ ዓለሙ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ባለችበት ቦታ ሁሉ የሚገኙትን የሚያጠቃልል ሲሆን በውጭ ሀገር የሚገኙትን አህጉረ ስብከት ለመምራትና ለማስተዳደር የሚያስችል የየሀገሮቹን ሕግጋተ መንግሥት ያገናዘበና ከዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን ጋር የተጣጣመ ፖሊሲናየመተዳደሪያ ደንብ በቅዱስ ሲኖዶስ እንዲወጣላቸው ይደረጋል፡፡

፪. ቤተ ክርስቲያን በሀገርም ሆነ በዓለም አቀፍ ደረጃ በየጊዜው እየተስፋፋችና የሐዋርያዊ ተልእኮ እንቅስቃሴዋም እየተጠናከረ በሔደ መጠን ተጨማሪ የሀገረ ስብከት ጽሕፈት ቤቶች በቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔ ይቋቋማሉ፡፡

### አንቀጽ ፵፯
### የሀገረ ስብከት መዋቅር

እያንዳንዱ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን

ሀገረ ስብከት የሚከተለው መዋቅራዊ አደረጃጀት ይኖረዋል፡፡

፩. የሀገረ ስብከት ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት
፪. ተጠሪነታቸው ለሀገረ ስብከቱ ሊቀጳጳስ የሆኑ

፫. የሀገረ ስብከት የሰበካ አስተዳደር ሥራ አስፈጻሚ

፬. የሀገረ ስብከት አስተዳደር ጉባኤ

፭. የሀገረ ስብከት ልዩ ልዩ የሥራ ክፍሎች

፮. የወረዳ ቤተ ክህነት ጽ/ቤት

፯. የወረዳው የሰበካ አስተዳደር መንፈሳዊ ጉባኤ ሥራ አስፈጻሚ

፰. የወረዳ ቤተ ክህነት ልዩ ልዩ የሥራ ዘርፎች

፱. የአጥቢያ ቤተ ክርስቲያን አስተዳደር ጽሕፈት ቤት

፲. የወረዳ ቤተክህነትና የአጥቢያ ቤተ ክርስቲያን ሊኖራቸው የሚገባው መዋቅራዊ አደረጃጀት በቃለ ዓዋዲ በዝርዝር ይወሰናል፡፡

## አንቀጽ ፵፱
## የቤተ ክርስቲያን የገቢ ክፍያ ሥርዓት

፩. እያንዳንዱ የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ካህናትና ምእመናን ዓሥራት በኲራትና የአባልነት ክፍያ የመክፈል ክርስቲያናዊ ግዴታ አለበት ፡፡

፪. የእያንዳንዱ አጥቢያ ቤተ ክርስቲያን ከተለያዩ

መንፈሳዊ፣ ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ የሥራ እንቅስቃሴዎች ከሚያገኘው ገቢ ቅዱስ ሲኖዶሱ በሚወስነው ፐርሰንት መሠረት ለወረዳው ቤተ ክህነት የክፍያ ድርሻውን ገቢ የማድረግ ኃላፊነት ሲኖርበት በተመሳሳይ የወረዳው ቤተ ክህነት ለአህጉረ ስብከት እንዲሁም አህጉረ ስብከቱ ለመንበረ ፓትርያርክ ጠቅላይ ቤተ ክህነት ገቢ ያደርጋሉ ፡፡

## አንቀጽ ፺
## የአዲስ አበባ ሀገረ ስብከት

፩. የአዲስ አበባ ሀገረ ስብከት የብፁዕ ወቅዱስ ፓትርያርክ ልዩ ሀገረ ስብከት ነው፡፡

፪. የአዲስ አበባ ሀገረ ስብከት በቅዱስ ፓትርያርኩ አቅራቢነት ተጠሪነቱ ለቅዱስ ፓትርያርኩ የሆነና በቅዱስ ሲኖዶሱ የሚመደብ ረዳት ሊቀጳጳስ ይኖረዋል፡፡

፫. የሀገሪቱ ርእሰ ከተማ ስለሆነና ከሌሎች አህጉረ ስብከት የሚለይባቸው ልዩ ሁኔታዎች ስላሉ እነዚህን ሁኔታዎች ከግምት ያስገባ ለየት ያለ አደረጃጀት በቃለ ዓዋዲው እንዲኖረው ይደረጋል፡፡

## አንቀጽ ፺፩
## የሀገረ ስብከት ቤተ ክህነት ዋና ጽሕፈት ቤት

፩. የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን የሀገረ ስብከት ዋና ጽሕፈት ቤት በሀገረ ስብከቱ ለሚገኘው የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር ከፍተኛ የሥራ አስፈጻሚ አካል ነው፡፡

፪. እያንዳንዱ ሀገረ ስብከት በቅዱስ ሲኖዶስ በተሾመ ኤጲስ ቆጶስ ወይም ሊቀጳጳስ ይመራል፡፡

፫. የሀገረ ስብከቱ ጽሕፈት ቤት የበላይ ተጠሪና መሪ የሀገረ ስብከቱ ኤጴስ ቆጶስ ወይም ሊቀጳጳስ ነው። ከእርሱም ቀጥሎ የመሪነት ኃላፊነቱ የሀገረ ስብከቱ ቤተ ክህነት ሥራ አስኪያጅ ይሆናል።
፬. ሀገረ ስብከቱ ዓላማውንና ተግባሩን የሚያስፈጽምባቸውና መንፈሳዊና ማኅበራዊ አገልግሎቱን የሚያከናውንባቸው ተጠሪነታቸው ለሀገረ ስብከቱ ሊቀጳጳስ የሆነ የሚከተሉት ዋና ዋና ክፍሎችና እንደ አስፈላጊነቱ ሊከፈቱ የሚችሉ ልዩ ልዩ የሥራ ዘርፎች ይኖሩታል። እነዚህም፡-

ሀ) የሀገረ ስብከት ሊቃውንት ጉባኤ
ለ) የስብከተ ወንጌል ዋና ክፍል
ሐ) የትምህርትና ማሠልጠኛ ክፍል
መ) የሰበካ ጉባኤ ማደራጃ ክፍል
ሠ) የሰንበት ትምህርት ቤቶች ማደራጃ ክፍል
ረ) የገዳማትና ቅርሳ ቅርስ ክፍል
ሰ) የሀገረ ስብከት መንፈሳዊ ፍርድ ቤት
ሸ) የሀገረ ስብከት የቁጥጥር አገልግሎት (ኦዲትና ኢንስፔክሽን)
ቀ) የሀገረ ስብከት የሥነ-ምግባርና ሥነ-ሥርዓት ክትትል ክፍል

የእነኚህና የሌሎችም ሥራ ዘርፎቹ ዝርዝርና የሚያከናውኗቸው ተግባራት በቃለ ዓዋዲው የሚገለፁ ይሆናል።

፭. የሀገረ ስብከቱ መንበረ ጵጵስናና ጽሕፈት ቤቱ ቅዱስ ሲኖዶስ ሀገረ ስብከት ብሎ በሰየመው ርእሰ ከተማ ይሆናል።
፮. የሀገረ ስብከቱ ዋና ጽሕፈት ቤት ተጠሪነት ለጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ነው።

## አንቀጽ ፶፪
## የሀገረ ስብከት ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ተግባርና ኃላፊነት

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን የሀገረ ስብከት ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል፡፡

፩. ከጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት የሚተላለፉትን የቅዱስ ሲኖዶስ ውሳኔዎችና ልዩ ልዩ መመሪያዎችን በቤተ ክርስቲያኒቱ ሕግጋት መሠረት ይፈጽማል፣ ያስፈጽማል፡፡

፪. በሀገረ ስብከቱ ክልል ውስጥ የሚገኙትን ገዳማት፣ አድባራትና የገጠር አብያተ ክርስቲያናት እንዲሁም የቤተ ክርስቲያኒቱን ተቋማት የወረዳ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤቶችንና የሀገረ ስብከቱ ልዩ ልዩ የሥራ ዘርፎች በቤተ ክርስቲያኒቱ ሕግጋት መሠረት ይመራል፣ ያስተዳድራል፣ ይቆጣጠራል፡፡

፫. በሀገረ ስብከቱ ውስጥ የሚገኙ ምእመናን በተደራጀና በተሟላ ሁኔታ የትምህርተ ወንጌል አገልግሎት እንዲያገኙና ስለሃይማኖታቸው በሚገባ እንዲያውቁ፣ በመንፈሳዊ ሕይወት እንዲጸኑና በሥርዓተ ቤተ ክርስቲያን እንዲመሩ ለማድረግ በትኩረት ይሠራል፣ ይከታተላል፡፡

፬. ሀገረ ስብከቱ ተልእኮውን ለመፈጸም የሚችልበትን የገቢ ምንጭ ለማስገኘት የሚረዱ የልማት ፕሮጀክቶችን እያጠና የቤተ ክርስቲያን ሀብትና ንብረት የሚለማበትን መንገድ ያመቻቻል፤ ሥራውንም በቤተ ክርስቲያኒቱ ሕግጋትና ደንቦች መሠረት ይፈጽማል፡፡

፭. በሀገረ ስብከቱ ውስጥ የሚንቀሳቀስ ማንኛውም የቤተ

ክርስቲያኒቱ ሀብትና ንብረት በቤተ ክርስቲያኒቱ የፋይናንስና የንብረት አስተዳደር ደንብ መሠረት የሚከናወን መሆኑንና ለቤተ ክርስቲያን አገልግሎት ብቻ መዋሉን ይቆጣጠራል።

፮. የየዓመቱን የሀገረ ስብከቱን የሥራና የአገልግሎት ዕቅድና በጀት አዘጋጅቶ ለጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት ያቀርባል፣ በዕቅዱ መሠረት የተከናወነውንም የዕቅድ አፈጻጸም ዘገባ በየዓመቱ ሪፖርት ያደርጋል።

፯. በሀገረ ስብከቱ ውስጥ በሚገኙ ወረዳዎች፣ ገዳማት፣ አድባራትና የአጥቢያ ቤተ ክርስቲያን እንዲሁም በልዩ ልዩ የሥራ ዘርፎች የሚገኘውን የሰው ኃይል የሥራ ዝውውር፣ ዕድገት፣ የሥነ-ሥርዓትና ሌሎች አስተዳደራዊ ጉዳዮችን በቤተ ክርስቲያኒቱ የሰው ሀብት አስተዳደር ደንብ መሠረት ያከናውናል፤ እንዲከናወንም ያደርጋል።

፰. በየዓመቱና አስፈላጊ ሆኖ በሚገኝበት ጊዜ በሀገረ ስብከቱ ውስጥ የሚገኙት ገዳማት፣ አድባራት፣ የገጠር አብያተ ክርስቲያናትና የልዩ ልዩ ተቋማት የፋይናንስና የንብረት አያያዝና በሂሣብ አጣሪ (ኦዶተር) እንዲመረመር ያደርጋል።

፱. በየደረጃው የሚገኙ የቤተ ክርስቲያን አገልጋዮች ስለ ቤተ ክርስቲያናቸው ነባራዊ ሁኔታዎች፣ ስለ መንፈሳዊ አገልግሎታቸውና ስለሚጠበቅባቸው መንፈሳዊ ግዴታ የሚማሩበትና የሚያውቁበት የዕውቀትና የክሂሎት ማበልጸጊያ ሥልጠናዎችን በየጊዜው እያዘጋጀ ተግባራዊ ያደርጋል፣

፲. በገጠር አብያተ ክርስቲያናት በገዳማትና በአድባራት ዙሪያ የሚገኙ ምእመናን መንፈሳዊ ደኅንነት እንዲጠበቅ፣ አገልግሎቶች እንዲጠናከሩና የምእመናን ቁጥር እንዲጨምር

በትኩረት ይሠራል፣ ሁኔታዎችንም ያመቻቻል።

፲፩. ከቅዱስ ሲኖዶስና ከጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት እየተወሰኑ የሚላኩለትን ሌሎች ተግባራትንም ከሊቀ ጳጳሱ መመሪያ እየተቀበለ ያከናውናል።

## አንቀጽ ፵፫
## የየሀገረ ስብከት ኤጲስ ቆጶስ፣ ጳጳስና ሊቀጳጳስ ተግባርና ኃላፊነት

የሀገረ ስብከት ኤጲስ ቆጶስ፣ ጳጳስናሊቀ ጳጳስ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል።

፩. የሀገረ ስብከት ኤጲስ ቆጶስ፣ ጳጳስናሊቀጳጳስ በሀገረ ስብከቱ ያለውን የቤተ ክርስቲያኒቱን አስተዳደር በኃላፊነት ይመራል።

፪. በሀገረ ስብከቱ ውስጥ በሚገኙት ገዳማት፣ አድባራትና የገጠር አብያተ ክርስቲያናት ውስጥ ላሉት ካህናትና ምእመናን መንፈሳዊ አባትና መሪ ነው።

፫. የቤተ ክርስቲያን ጥንታዊነትና ታሪካዊነት፤ የሀገር ፍቅርና አንድነት በሰላም ተጠብቆ እንዲኖር እንዲሁም የኦርቶዶክሳዊት ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን እምነት ተከታዮች ሃይማኖታቸውን፣ ሥርዓተ ቤተ ክርስቲያናቸውን እና ኦርቶዶክሳዊ ትውፊታቸውን ጠብቀው እንዲኖሩ ብርቱ ጥበቃ ያደርጋል።

፬. በፍትሕ መንፈሳዊ አንቀጽ ፯ እና ፯ በተደነገገው መሠረት በሥነ-ምግባራቸው የተመሰገኑትንና በትምህርት ደረጃቸው ብቁ የሆኑትን ዕጩዎች በመፈተን እያጣራ ከመካከላቸው ቀሳውስትንና ዲያቆናትን ይሾማል።

፭. በዚህ ሕግ አንቀጽ ፳፰(፭) የተደነገገው እንደተጠበቀ ሆኖ በሙያቸው ብቁ የሆኑትንና በግብረ-ገብነታቸው የታወቁትን የገዳማትና የአድባራት አስተዳዳሪዎችን እያጠናና እያስጠና ብቁ ሆነው ሲገኙ ይሾማል፡፡ የአንድነት ገዳማትን በተመለከተ ግን እንደ ገዳማቸው ሕግ ወይም በደንባቸው መሠረት መርጠው ያቀረቧቸውን አበምኔቶች (እመምኔቶች) ሹመት ተቀብሎ ያፀድቃል፡፡

፮. በሀገረ ስብከቱ ውስጥ የሚገኙትን አብያተ ክርስቲያናት በሚመለከት ከሀገረ ስብከቱ ሥራ አስኪያጅና ከአስተዳደር ጉባኤው ጋር እየመከረ በሀገረ ስብከቱ ከሚገኙት መንግሥታውያንና ሕዝባውያን ድርጅቶች ጋር የጽሑፍም ሆነ የቃል ግንኙነት በማድረግ ሥራውን ያከናውናል፡፡

፯. በሀገረ ስብከቱ ያለውን የአስተዳደር ጉባኤ በሊቀመንበርነት ይመራል፡፡

፰. በትምህርት ችሎታውና በሥራ ልምዱ ለሀገረ ስብከት ሥራ አስኪያጅነት ብቁ የሆነውን ሰው መርጦ ለጠቅላይ ሥራ አስኪያጅ በማቅረብ ቅዱስ ፓትርያርኩ ሲስማማበት በጠቅላይ ቤተ ክህነት ሥራ አስኪያጅ ፊርማ እንዲሾም ያደርጋል፡፡ ለሥራ አስኪያጅነት ዕጩ ሆኖ ሊቀርብ የሚችለው የሚከተሉትን መሥፈርቶች የሚያሟላ መሆን ይኖርበታል፤

ሀ/ ዕድሜው ከ፴፭-፶፭ (ከሠላሳ አምስት እስከ ሐምሳ አምስት) የሆነው፤

ለ/ ሥልጣነ ክህነት ያለውና ማስተማር የሚችል፤

ሐ/ ከቤተ ክርስቲያኒቱ አብነት ት/ቤቶች በአንድ ትምህርት

ወይም ከመንፈሳውያን የከፍተኛ የትምህርት ተቋማት (ኮሌጆች) የተመረቀ፤

መ/ ቢቻል በአስተዳደር ሙያ ቢያንስ ዲፕሎማ ያለው፤በሚመደብበት ሀገረ ስብከት የሚገኙ ቋንቋዎችን መናገር የሚችል፡፡

፱. በሀገረ ስብከቱ ስም በባንክ የሚገኘውን የቤተ ክርስቲያኒቱን ገንዘብ ከሥራ አስኪያጁ ጋር በጣምራ ፊርማ ያንቀሳቅሳል፡፡

፲. በሀገረ ስብከቱ የሚገኙትን የልዩ ልዩ ክፍሎች ኃላፊዎችንና ሠራተኞችን በቤተ ክርስቲያኒቱ የሠራተኛ አስተዳደር ደንብ መሠረት አወዳድሮ በሀገረ ስብከቱ የአስተዳደር ጉባኤ እያስወሰነ ይመድባል፤ አመዳደቡንም ለጠቅላይ ቤተክህነት ያሳውቃል፡፡

## <u>አንቀጽ ፶፩</u>
## <u>የሀገረ ስብከት ቤተ ክህነት ሥራ አስኪያጅ ተግባርና ኃላፊነት</u>

በዚህ ሕግ አንቀጽ ፶፫(፰) መሠረት የሚሾመው የሀገረ ስብከት ሥራ አስኪያጅ ተጠሪነቱ ለሀገረ ስብከቱ ሊቀጳጳስ ሆኖ የሚከተሉት ተግባራትና ኃላፊነቶች ይኖሩታል፡፡

፩. በሀገረ ስብከቱ ዓመታዊ የድርጊት መርሐ-ግብር መሠረት በመላ ሀገረ ስብከቱ የትምህርተ ወንጌል ሥርጭት የሚስፋፋበትን ምቹ ሁኔታ ይፈጥራል፡፡

፪. በሀገረ ስብከቱ በሚገኙ ወረዳዎች የስብከተ ወንጌል አገልግሎት በአግባቡ እንዲዳረስ ተገቢውን ክትትል ያደርጋል፣ እርሱም ያስተምራል፡፡

፫. በሀገረ ስብከቱ የሚገኙ የገዳማትና አድባራት እንዲሁም የገጠር አጥቢያ አብያተ ክርስቲያናት አስተዳዳሪዎች በልዩ ልዩ የቤተ ክርስቲያን አስተዳደር ጉዳዮች ላይ ትምህርትና ስልጠና እንዲያገኙ ያደርጋል። የሥልጠናውንም ሒደት እየተገኘ ይገመግማል፣ ይቆጣጠራል።

፬. በሀገረ ስብከቱ ውስጥ በሚገኙ አብያተ ክርስቲያናት ውስጥ የአብነት ትምህርት ቤቶች እንዲጠናከሩና በሌለባቸውም እንዲቋቋሙ ይሠራል፣ ክትትልም ያደርጋል።

፭. በሀገረ ስብከቱ የሚገኙ የካህናት ማሠልጠኛዎች ከመደበኛ ሥርዓተ ትምህርታቸው በተጨማሪ የቤተ ክርስቲያንን ችግር የሚፈቱ ካህናትን የሚያወጡ እንዲሆኑ ይሠራል፤ ክትትልም ያደርጋል።

፮. በየጊዜው በቅዱስ ሲኖዶስ የሚወሰኑት መመሪያዎችና ከጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት የሚተላለፉት ትእዛዞች ሁሉ እንዴት መፈጸም እንዳለባቸው ከመፈጸማቸው በፊት ለሊቀጳጳሱ እያሳወቀ ይፈጽማል፤ ያስፈጽማል።

፯. ሊቀጳጳሱ በተለያየ ምክንያት በማይገኝበት ጊዜ የሀገረ ስብከቱን የአስተዳደር ጉባኤ የመነጋገሪያ አጀንዳዎችን (ርእሰ ጉዳዮችን) በቅድሚያ ለሊቀጳጳሱ በማሳወቅ ስብሰባውንም በሊቀመንበርነት ይመራል።

፰. በበጀት የተመደበውን የሀገረ ስብከቱን ገንዘብና ንብረት ከሊቀጳጳሱ መመሪያ እየተቀበለ ያንቀሳቅሳል።

፱. የሀገረ ስብከቱን የሚንቀሳቀሱና የማይንቀሳቀሱ ንብረቶች በቤተ ክርስቲያኒቱ የንብረት አስተዳደር ደንብ መሠረት ያስተዳድራል፣ ይጠብቃል፣ ያስጠብቃል።

፲. የሀገረ ስብከቱን ዓመታዊ የሥራ እቅድና በጀት አዘጋጅቶ በአስተዳደር ጉባዔው ያቀርባል፡፡ሲጸድቅም ለጠቅላይ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት በማሳወቅ ተግባራዊ ያደርጋል፡፡

፲፩. የዕቅድ አፈጻጸም ዘገባን በየሦስት ወሩ ለአስተዳደር ጉባዔው ያቀርባል፡፡
፲፪. በቤተ ክርስቲያኒቱ የሰው ኃይል አስተዳደር ደንብ መሠረት የሀገረ ስብከቱን ሠራተኞች ያስተዳድራል፡፡ ይሁንና ከሊቀጳጳሱ መመሪያ ሳይቀበል ሠራተኛ መቅጠር፣ዝውውር፣ ደመወዝ መጨመርና ሠራተኛ ማሰናበትን የመሳሰሉት ተግባራን መፈጸም አይችልም፡፡

፲፫. በሀገረ ስብከት ደረጃ የሰበካ መንፈሳዊ አስተዳደር ጉባዔና የሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴው ሊቀመንበር እንደመሆኑ መጠን የመንፈሳዊ ጉባዔው ውሳኔዎች ለወረዳ ቤተ ክህነት ጽሕፈት ቤት በማስተላለፍ በየደረጃው ለሚገኙ አቢያተ ክርስቲያናት የሰበካ መንፈሳውያን ጉባኤያት እንዲደርሱ ያደርጋል፣ አፈጻጸማቸውን ይከታተላል፡፡

፲፬. ማንኛውም የሀገረ ስብከቱ ወጪና ገቢ በቤተ ክርስቲያኒቱ የፋይናስና የንብረት አስተዳደር ደንብ መመሪያ መሠረት መከናወኑን ይከታተላል፣ ይቆጣጠራል፡፡

፲፭. የሀገረ ስብከቱን የሥራ ክፍሎች ሁሉ የዕቅድ አፈጻጸም እየገመገመ ለሊቀጳጳሱ ዘገባ ያቀርባል፡፡

፲፮. በሀገረ ስብከቱ የሚገኙ አብያተ ክርስቲያናት የሥራ እንቅስቃሴ በወረዳው ቤተክህነት ጽሕፈት ቤቶች አማካኝነት ይከታተላል ይቆጣጠራል፡፡

፲፯. በሁሉም መስክ የቤተ ክርስቲያኒቱ ልዩ ልዩ የመረጃ ቅንብር (ስታቲስቲካዊ) መረጃ ተጠናክሮና ተመዝግቦ እንዲገኝ የሚመለከተውን የሥራ ክፍል በማገዝ ይሠራል።

፲፰. ከሀገረ ስብከቱ ሊቀጳጳስ የሚሰጡትን ተጨማሪ ሥራዎች ያከናውናል።

## ምዕራፍ ዐራት
## አንቀጽ ፶፰
## ሕገ ቤተክርስቲያንን ስለማሻሻል

፩. ይህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን በቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባዔ ውሳኔ አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ሊሻሻል ይችላል።

፪. ከሦስት አንድ እጅ (1/3ኛ) የሚሆኑ የቅዱስ ሲኖዶስ አባላት የማሻሻያ ጥያቄ ሲያቀርቡና በቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባዔ ውሳኔ አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ ሊሻሻል ይችላል።

## አንቀጽ ፶፱
## የመሸጋገሪያ ድንጋጌ

በዚህ ሕግ ያልተካተቱና ወደፊት ሌላ ዝርዝር ሕግ ይወጣላቸዋል ተብለው ተለይተው የተመለከቱ ጉዳዮች እነዚህ የተባሉት ዝርዝር ሕጎች እስኪወጡ ድረስ ከዚህ ሕግ መጽናት በፊት ይሰራበት በነበረው ሕግ መሠረት መተዳደር ይቀጥላሉ።

## አንቀጽ ፶፱
## የማይጸኑ (የተሻሩ) ሕጎች

፩. ከላይ በአንቀጽ ፶፰ የተጠቀሰው እንደተጠበቀ ሆኖ ከዚህ

በፊት ግንቦት ፲ ቀን ፲፱፻፺፩ ዓ.ም. በቅዱስ ሲኖዶስ ወጥቶ ሲሠራበት የነበረው ሕገ ቤተ ክርስቲያን በዚህ ሕገ ቤተ ክርስቲያን ስለተተካ ተሽሯል፡፡

፪. ከላይ በአንቀጽ ፶፯ የተጠቀሰው እንደተጠበቀ ሆኖ በሥራ ላይ ያሉም ሆኑ ወደፊት የሚወጡ ደንቦች፣ መመሪያዎችና ልማዳዊ አሠራሮች ይህን ሕገ ቤተክርስቲያን የሚፃረሩ ከሆነ ተፈጻሚነት የላቸውም፡፡

## አንቀጽ ፶፰
## ሕጉ የሚጸናበት ጊዜ

ይህ ሕግ በቅዱስ ሲኖዶስ ምልዓተ ጉባዔ ከጸደቀበት ከጥቅምት ፳፻፲ ዓ.ም. ጀምሮ የጸና ይሆናል ፡፡

የኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን
ቅዱስ ሲኖዶስ
ጥቅምት ፳፻፲ ዓ.ም. አዲስ አበባ




በኢትዮጵያ ኦርቶዶክስ ተዋሕዶ ቤተ ክርስቲያን ሥር
በየደረጃው የሚገኙት የሰበካ መንፈሳውያን ጉባኤያት አጠቃላይ መዋቅር

በትንሣኤ ዘጉባኤ ማተሚያ ቤት ታተመ